# ክፍል ፪

## የመኰንን ሀብተወልድ

## እና

## የወልደጊዮርጊስ ወልደ ዮሐንስ

# አነሳስና የሥልጣን ዘመን

# ምዕራፍ ፩

## መኰንን ሀብተወልድ

በአባታቸው መንዝ፣ በእናታቸው ይፋት የሆኑትና የእንጦጦ ቅዱስ ራጉኤል ቤተክርስቲያን ትክለኛ የነበሩት አለቃ ሀብተወልድ ሀብቴነህ፣ የቡልጋ ተወላጅ የሆኑትን ወይዘሮ ያደግድጉ ፍልፍሉን አግብተው ሲኖሩ፣ ስምንት ልጆች ወልደው ነበር። እነዚህ የመንዝና የቡልጋ ተወላጆች፣ ከአዲስ አበባ ዐርባ አምስት ኪሎ ሜትር ርቆ በሚገኘው በአድዓ ወረዳ "ደንቢ" በተባለው ቀበሌ ትዳራቸውን ከመሠረቱ በኋላ፣ "ደብሪቱ" ከተባለችው ከመጀመሪያዋ ሴት ልጃቸው ቀጥሎ ጥቅምት 19 ቀን 1886 ዓ.ም ወንድ ልጅ ሲወለድ፣ ስሙን "መኰንን" ብለው ጠሩት። በሰሜን ሸዋ ቤተሰቦች ዘንድ፣ የሕግ ጋብቻ ከተፈጸመ በኋላ፣ መጀመሪያ ሴት ልጅ ከተወለደችና ተከታዩ ደግሞ ወንድ ልጅ ከሆነ፣ መልካም ዕድልና ሲሣይ ነው ተብሎ ስለሚታመን፣ የደብሪቱና የመኰንን በቅደም ተከተል መወለድ፣ ለአለቃ ሀብተወልድና ለወይዘሮ ያደግድጉ፣ ከፍተኛ ደስታ ሰጥቷቸው እንደነበረ ይነገራል።

የመኰንን አባት አለቃ ሀብተወልድ፣ ከአያታቸው ከአለቃ ወልደማርያም፣ ቀጥሎም ከአባታቸው ከአለቃ ሀብቴነህ ሲያያዝ እንደመጣው የእንጦጦ የቅዱስ ራጉኤልን ደብር በማገልገል ታዋቂ በመሆናቸው፣ ዳግማዊ አፄ ምኒልክ በአድዓ ወረዳ ውስጥ፣ በሚገኘው "ጨለባ" በተባለው ቀበሌ አንድ ጋሻ የማደሪያ መሬት ሰጧቸው። ነገር ግን አባታቸው አለቃ ሀብቴነህ ሲሞቱ፣ በዚሁ በአድዓ ወረዳ "ደንቢ" ላይ የነበራቸውን አንድ ጋሻ መሬት ከሁለት እህቶቻቸው ጋር እንዲከፋፈሉ ስለተናዘዙላቸው፣ አለቃ ሀብተወልድ ትዳራቸውን መሥርተው ስምንት ልጆች የወለዱትና እስከ ዕለተ ሞታቸው ድረስ የኖሩት፣ በዚሁ በውርስ ባገኙት ርስታቸው ላይ ነበር።

የአለቃ ሀብተወልድ የወንዶች ልጆች መጀመሪያ የሆነው መኰንን፣ በተወለደበት ቦታ የአማርኛን ጽሕፈትና ንባብ ተምሮ ዳዊት ከደገመ በኋላ፣ ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ዝቋላ ወንበር ማርያም ተልኮ፣ ግዕዝን፣ ዜማና ቅኔን፣ ድጓና ጾመ ድጓን፣ በዐሥራ አምስት ዓመቱ ተምሮ አጠናቀቀ። የአለቃ ሀብተወልድ ፍላጐት ልጃቸው መኰንን የእሳቸውን መስመር ተከትሎ በቤተክርስቲያን ሥርዓት እንዲያድግ ስለሆነ፣ ከዝቋላ በኋላ ወዲያውኑ ወደ እንጦጦ ቅዱስ ራጉኤል ደብር ሄዶ፣ የዲቁና አገልግሎት እንዲሰጥ አደረጉ።

በ1902 ዓ.ም ዳግማዊ አፄ ምኒልክ ታመው በእንጦጦ ማርያም ቤተክርስቲያን ጠበል በሚጠመቁበት ጊዜ፣ የጸሎት መጻሕፍት አንባቢዎች የሚሆኑ ዲያቆናት ከየቤተክርስቲያኑ ሲፈለጉ፣ ከራጉኤል ደብር መኰንን ሀብተወልድና ታከለ ወልደሐዋርያት ችሎታ ያላቸው ናቸው ተብለው ተመረጡ። ዲያቆን ታከለ ወልደሐዋርያት (ኋላ ደጃዝማች) የአለቃ ሀብተወልድ የእህት ልጅ ሲሆን፣ ከዲያቆን መኰንን ሀብተወልድ ጋር የታላቅና የታናሽ ልጆች መሆናቸው ነው። እነዚህ በዕድሜ የሚቀራረቡትና የአንድ አያት ልጆች የሆኑት ዲያቆናት፣ አፄ ምኒልክ

ጠበሉን በሚጠመቁበት ጊዜ በሚያስሙት ጣዕም ያለው የንባብ ቃና፣ ከሊቀ ዳዳሱና ከእጨጌው አድናቆት በማግኘታቸው እቴጌ ጣይቱ ሸልማት ሰጥተዋቸዋል።

ዲያቆን መኰንን ሀብተወልድ በእንጦጦ ማርያም አፄ ምኒልክን በማስታመም አንድ ዓመት ያህል ቆይተው ወደ ራጉኤል ሲመለሱ፣ ብርቱ የብርድ ሕመም አድሮባቸው ብዙ ቀን ታመሙ። ለዚህ ሕመማቸው ወደ ቆላ አገር ቢሄዱ ይሻላቸዋል ስለተባለ፣ የአባታቸው ወዳጅ በሆኑት በእጨጌ ወልደጊዮርጊስ እርዳታ፣ በአሩሲ (ዛሬ አርሲ) አውራጃ ውስጥ በኩ ወደተባለው ሞቃት ወረዳ ተዛውረው የገበያና የአሥራት* ጸሐፊ በመሆን እየሠሩ መኖር ጀመሩ።

መኰንን ሀብተወልድ በአሩሲ አውራጃ ሦስት ዓመት በቆዩበት ጊዜ፣ የታወቁት ካህን የአለቃ ቤዛ ልጅ የሆኑትን ወይዘሮ በላይነሽ ቤዛን አግብተው፣ ጥላሁንና ከበደ የተባሉትን ሁለት ወንዶች ልጆች ከወለዱ በኋላ፣ የመጀመሪያው ልጃቸው ጥላሁን በሕፃንነቱ በፈንጣጣ በሽታ ሲሞት፣ ሁለተኛው ከበደ፣ ከዚሁ ሕመም ተርፎ አደገላቸው።

## መኰንን፣ በጠና ታመሙ

ከፍ ብሎ እንደተገለጸው፣ አቶ መኰንን በአሩሲ በሚኖሩበት ጊዜ አባታቸው አለቃ ሀብተወልድና እናታቸው ወይዘሮ ያደግድጉ፣ እንዲሁም እህቶቻቸውና ወንድሞቻቸው ስለናፈቋቸው፣ እነርሱን ለማየት ጥቂት ቀናት ተጉዘው ከተወለዱበትና ካደጉበት "ደንቢ" ሲደርሱ፣ አገሩ ውስጥ በገባው የተስቦ በሽታ ምክንያት ብዙ ሰዎች ታመው፤ በሕይወትና በሞት መካከል ያጣጥሩ ነበር። ከቤታቸውም ሲገቡ ተከታይ እህታቸው ወይዘሮ የሺእመቤትና ሁለቱ ወንድሞቻቸው ሣህሉና ቀፀላ በዚሁ በተስቦ በሽታ ሞተው፣ አባትና እናታቸው በጠቅላላውም ቤተሰቡ በኃዘን ማዕበል ተውጠው አገኟቸው።

አለቃ ሀብተወልድና ወይዘሮ ያደግድጉ፣ በተአምር በሽታው ስላልያዛቸው ከሞት የተረፉትን ልጆቻቸውን ጉንበስ ቀና እያሉ በሚያስታምሙበት በዚያ አስቸጋሪ በሆነ ሰዓት፣ የመኰንን መምጣት ከፍ ያለ ጭንቀት ላይ ጣላቸው። ‹‹መኰንን መምጣት አልነበረበትም፤ አሁንም በቶሎ ወደ አሩሲ ቢመለስ ይሻላል ›› እያሉ ሲወተውቱ፣ በአንድ ሌሊት አዳር መኰንንም በበሽታው ተለክፈው አልጋ ያዙ። የሚቀጥ የወይዘሮ የሺእመቤት ቀጥታ ተከታይ የሆኑት ወይዘሮ ይመኙሻል ሀብተወልድ እንደምንም ድነው ከአልጋ ተነሥተዋል። ሌሎቹም ትንንሾቹ ልጆች፣ መኩብብ፣ አካለወርቅና፣ አክሊሉ ሀብተወልድ በሽታው ስላልጠናባቸው ተጠናክረዋል። የአቶ መኰንን ሕመም ግን፣ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየበረታ ሄደ። አዲስ አበባ የሚገኘው ዳግማዊ ምኒልክ ያቋቋሙት የፈረንጆች ሕክምና መስጫ፣ ለዚህ ለተስቦ በሽታ ፍቱን የሆነ መድኃኒት እየሰጠ ያድናል የሚል ወሬ ሲሰሙ፣ አለቃ ሀብተወልድ የታመመውን ልጃቸውን በቃሬዛ* ይዘው ሲገሠግሡ አዲስ አበባ ደረሱ። ሐኪሞቹ የአቶ መኰንን ሕመም ተስፋ የሌለው መስሎ ቢታያቸውም፣ የተቻላቸውን ለማድረግ በሽተኛውን ተቀብለው ማከም ጀመሩ። ነገር ግን አንድ

---

* የታክስ ግብር መሰብሰብ

* አልጋ

ሳምንት ያህል ሳያቋርጥ የተደረገው ሕክምና በታመመው በመኰንን ላይ ምንም ዓይነት ለውጥ ባለማሳየቱ፣ አለቃ ሀብተወልድ ተስፋ ቆርጠው ልጃን ይዤ ወደ አገሬ (ደንቢ) ልመለስ ብለው ተነሡ። ሐኪሞቹ ትንሽ ይታገሡ እያሉ በሚመክሯቸው ሰዓት፣ በድንገት አንድ ሰው እየሮጠ መጥቶ፣ ከእማሆይ አጥሩዘባ መልዕክት ይዤ መጥቻለሁ ብሎ አለቃ ሀብተወልድን ከሐኪሞቹ ቢሮ ይዟቸው ወደ ውጭ ወጣ። እማሆይ አጥሩዘባ፣ የደብረኃይል ቅዱስ ራጉኤል ታዋቂ ደብተራ የሚቹ የአለቃ ወልደተክሌ ባለቤት የነበሩ ናቸው። ለወዳጃቸው ለአለቃ ሀብተወልድ የላኩት መልዕክት፣ ከአንድ ቀን በፊት በሕልማቸው የታያቸውን ለማሳወቅ ነበር።

**« .... በሕልሜ የታመመውን ልጅህን ማማ* ላይ ቆሞ ወፍ ሲያባርር አይቼው ስገረም፣ አንድ መልአክ የመሰለ ሰው በድንገት አጠገቤ መጥቶ፣ ስሚ ! ይለኛል። ይህ የምታይው ልጅ ወደፊት የመንግሥት ሹም፣ የንጉሥ ባለሟል፣ የንጉሥ ታማኝ ይሆናል። ሰዎች አይበላ-አያስበላ የሚል ስም ያወጡለታል። የዕድሜ ጸጋ ያገኛል። ግን ሕመም አይገድለውም ... »** ብሎኝ ከአጠገቤ ተሠወረ። ለሕልሜ ፈች አያስፈልገውም ግልጽ ነው። ይልቁንስ እኔ የምመክርህን ስማኝ ! መኰንን እዚያው ሐኪሞቹ ዘንድ ይቆይ ! ሲሻለው ሥጋው ወደሙ እንዲቀበል አድርግ ! ወደፊት የአሩሲውን ኑሮ ትቶ በዚያው በንጉሡ ከተማ ጉጆ ያብጅ ! ለእኔ እንደሚታየኝ መኰንን ትልቅ ሰው ሆኖ ስምህን ያስጠራል። ግን፣ እኔና አንተ አንደርስበትም፤ አናየውም።

ይህንን እማሆይ አጥሩዘባ ያዩትን ሕልም፣ አለቃ ሀብተወልድ የተቀበሉት በደህና መንፈስ ነበር። አጋጣሚም ሆኖ ይህ መልዕክት በደረሳቸው ማግሥት፣ እንደበታቸው በትኩሳት ኃይል ተዘግቶባቸው የነበሩት ሕመምተኛው ልጃቸው፣ ቀና ብለው የመናገር ድምፅ አሰሟቸው። ቀጥሎም እንደ በድን የሆነውን ሰውነታቸውን ማንቀሳቀስ ጀመሩ። በዚህ ጊዜ፣ አለቃ ሀብተወልድ በጣም ተደስተው፣ እማሆይ አጥሩዘባ ባሳሰቡት መሠረት፣ ጥቅምት 19 ቀን (መኰንን በተወለዱበት ዕለት) አዲስ አበባ በሚገኘው በመንበረ መንግሥት ቅዱስ ገብርኤል ቤተክርስቲያን ያሉትን ካህናት ለምነው፣ ሆስፒታሉ ድረስ መጥተው አቆረቧቸው። ከዚህ በኋላ ደግሞ ታማሚው መኰንን በጣም ተሽሏቸው ከአልጋቸውም እየተነሡ ጠዋትና ማታ የጸሎት መጻሕፍት ሲያነቡ መታየት ጀመሩ። ይህንን እንደ ተአምር አድርገው የቆጠሩት አባታቸው አለቃ ሀብተወልድና እናታቸው ወይዘሮ ያደግድጉ፣ **« ... እኛ ከዚህ የበለጠ ደስታ ሊኖረን ስለማይችል፣ ፈጣሪያችንን ዕድሜ ጨምርልን ብለን አናስቸግረውም። መኰንን ድኖ ከቆመልን፣ የልጆቻችን አባት፣ የንብረታችን ኃላፊ ሆኖ ስማችንን ያስጠራልናል .... »** እያሉ፣ ጸሎታቸውን ማጠንከር ቀጠሉ።

እንግዲህ ! መኰንን ከሕመሙ ተርፈው ከሆስፒታል ከወጡ በኋላ ለወደፊት ሕይወታቸው መንገዱ ምንድን ነው ? ..... እማሆይ አጥሩዘባ ባሳሰቡት መሠረት፣ አሩሲ እንዳይመለሱ ተወስኖባቸዋል። በተጨማሪም፣ ባለቤታቸው ወይዘሮ በላይነሽ ቤዛ፣ የአቶ መኰንንን በጠና መታመም መልዕክተኛ ተልኮ ቢነገራቸውም፣ ሕፃን ልጅ ትቼ? በሚል ሰበብ መጥተው ባለመጠየቃቸው ቤተሰቡ በሙሉ ቂም ይዞባቸዋል። ስለዚህ አለቃ ሀብተወልድ በራሳቸው ሥልጣን የሚከተለውን ውሳኔ አደረጉ።

* እንደ ቆጥ ተሠርቶ አረኞች ሰብል የሚጠብቁበት ነው።

1ኛ/ መኰንን ከእንግዲህ ወዲህ አሩሲ ስለማይመለሱ፣ ባለቤታቸውን እንዲፈቱ ፍቺውንም ሰዎች ተላልከው እንዲፈጽሙት፣

2ኛ/ ሕፃኑ ልጅ፤ ከበደ ከአሩሲ ወደ ደንቢ መጥቶ አያቶቹ ዘንድ እንዲያድግ፤

3ኛ/ መኰንን ደህና ሥራ አግኝተው ኑሮአቸው እስከሚሟላ ድረስ የጓደኛቸው የአለቃ ደስታ ልጅ አቶ በቀለ ደስታ የአዲስ አበባ ፍልውሃ መጠመቂያ የገንዘብ ቤት ሹም ስለሆኑ፣ የማረፊያ ቤት እንዲሰጧቸውና እንዲረዷቸው፣ አድርገው ወደ መኖሪያቸው ወደ ደንቢ ተመለሱ።

## መኰንን ሀብተወልድ የፍልውሃ መግቢያ ገንዘብ ተቀባይ፣

የአለቃ ሀብተወልድ ጓደኛ ልጅ አቶ በቀለ ደስታ፣ የተጣለባቸውን አደራ በማሰብ፣ ጊዜ ሳይወስዱ መኰንን የፍልውሃ መግቢያ ገንዘብ ተቀባይ (ካርኔ ቆራጭ) ሆነው እንዲሠሩ ከበላዮቻቸው አስፈቅደው ቀጠሯቸው። ይህ ሥራ አሩሲ ከነበራቸው ከገበያ ቀረጥና ከአሥራት ግብር ጭቅጭቅ፣ እጅግ የተሻለ ከመሆኑም በላይ፣ የወር ደሞዛቸው በእጥፍ ስለአደገ፣ መኰንን ሀብተወልድ አዲሱን ሕይወታቸውን የጀመሩት በጋለ የደስታ መንፈስ ሆነ። በተጨማሪም የቤት ኪራይ ወጭ እንዳይኖርባቸው፣ አለቃቸው አቶ በቀለ አዲስ አበባ ካላቸው ንብረት አንዱን ቤታቸውን ለማረፊያ ስለሰጧቸው፣ ከፍተኛ እርዳታ አግኝተዋል። አሩሲ ያሉት ባለቤታቸው ወይዘሮ በላይነሽም፣ አቶ መኰንን አዲስ አበባ መኖር የተገደዱት በጤና ምክንያት መሆኑን በመረዳት፣ ፍቺውን ለመቀበልና ልጃቸውን ከበደን ወደ አያቶቹ ወደ ደንቢ ለመላክ መስማማታቸውን በመልዕክት ስለገለጹላቸው፤ ችግር ይፈጠራል ብለው የሠጉበት ጉዳይ ሁሉ ሰላም ሆነላቸው።

አቶ መኰንን፣ ቀደም ሲል እንደተገለጸው ምንም እንኳ በአገራችን ትምህርት የጠለቀ ዕውቀት ቢኖራቸውም፣ አሁን ለተሰጣቸው የገንዘብ ተቀባይነት ሥራ ዘመናዊውን የሒሳብ ማከናወኛ የሆኑትን አራቱን መደቦች፣ መደመርንና መቀነስን፣ ማብዛትንና ማካፈልን ባለማወቃቸው፣ በገቢ ሒሳብ አያያዝ በኩል ችግር ነበረባቸው። ሆኖም የተፈጥሮ ብልህነትና ትጋት ስላላቸው፣ የየዕለቱን ገቢ ለየብቻ በመያዝ፣ ከዚያም የየሳምንቱንና የወሩን ጠቅላላ ገቢ በጥሬ ባቄላ እየቆጠሩ በማዳመር፣ ትክክለኛውን የገቢ ሒሳብ በየሠላሳዎቹ ቀናቶች ለማቅረብ በመቻላቸው፣ አለቃቸውን አስደሰቱ።

መኰንን ሀብተወልድ፣ በዚህ በፍልውሃ መግቢያ የገንዘብ ተቀባይነት ሥራ በየቀኑ ከንጋቱ ዐሥራ አንድ ሰዓት ጀምሮ እስከ ቀኑ ስድስት ሰዓት ድረስ በመሥራት አንድ ዓመት ካሳለፉ በኋላ፣ በየጊዜው ፍልውሃ ለመጠመቅ ሲመጡ ያወቋቸው አርመኖችና ግሪኮች የሰጧቸውን ምክር በመከተል፣ ከሰኞ እስከ ዓርብ ዘወትር ግማሽ ቀን "አሊያንስ ፍራንሴዝ" በተባለው ተማሪ ቤት ገብተው፣ ፈረንሣዊኛና የአራት መደብ የሒሳብ ትምህርት ለመማር እንዲፈቀድላቸው ማመልከቻ አቀረቡ። አለቃቸው አቶ በቀለም፣ መኰንን ጠንካራና ታታሪ በመሆናቸው የአራት መደብ የሒሳብ አሠራር ከተማሩ፣ መሥሪያ ቤቱን የበለጠ

ይጠቅማሉ በሚል አስተሳሰብ፣ ዘወትር ከእኩለ ቀን በኋላ ያላቸውን ጊዜ በትምህርት እንዲያሳልፉ ፈቀዱላቸው።

መኰንን ሀብተወልድ ይህንን ጥሩ ዕድል በማግኘታቸው፣ በአሊያንስ ፍራንሴዝ ወዲያውኑ ተመዝግበው፣ የፈረንሣዊኛ ቋንቋና የሒሳብ ትምህርታቸውን መከታተል ቀጠሉ። በሁለት ዓመት ተኩል ጊዜ ውስጥ ያጠኗቸው የፈረንሣዊኛ ቃላቶች፣ በጣም አስፈላጊ ለሆኑ አንዳንድ ጉዳዮች ሐሳባቸውን ለመግለጥ ስለአስቻላቸውና፣ በሒሳብ በኩልም አራቱን መደብ ብቻ ሳይሆን ከዚያም ትንሽ ከፍ ብሎ በሠንጠረዥ የሒሳብ አሠራር በማወቃቸው፣ ከእንግዲህ ወዲህ ከፍልውሃ መግቢያ ካርኔ ቆራጭነት ወደተሻለ የቢሮ ሥራ ለመዛወር ችሎታቸው አስተማማኝ ሆኖ ታያቸው።

ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፣ እነዚያ የፍልውሃ ደንበኞቻቸው የሆኑት ግሪኮችና አርመኖች፣ " ባቁላ እየቆጠሩ " ሒሳብ ከመሥራት አሊያንስ ፍራንሴዝ ገብተው እንዲማሩ እንደመከሯቸው ሁሉ፣ አሁንም በዚህ በሁለት ዓመት ተኩል ውስጥ በገበዩት ዕውቀት፣ ደህና ሥራ ለማግኘት ለጉምሩክ ዋና መሥሪያ ቤት እንዲያመለክቱ አበረታቷቸው። በዚህ ምክር መሠረት መኰንን፣ የሥራ ልምዳቸውንና በአሊያንስ ፍራንሴዝ ያጠኑትን ገልጸው ማመልከቻቸውን ባቀረቡ በአንድ ሳምንት ጊዜ ውስጥ፣ የላጋር ጉምሩክ ዲሬክተሩ ጠርተው ከነገ ጀምሮ የሒሳብ ክፍል ረዳት ሆነህ እንድትሠራ ቀጥሬሃለሁ አሏቸው። በዚህ ጊዜ፣ መኰንን ሀብተወልድ ወዲያውኑ እጅ ነሥተው በመቀበል ፋንታ፣ « ጌታዬ ያደረጉት ፈጣን ውሳኔ ለእኔ ለአመልካቹ በጣም ሊያስደስተኝ የሚገባ ቢሆንም፣ ደንቡን በመከተል ሳልፈተንና ችሎታዬ ሳይረጋገጥ ነገውኑ ሥራ ብጀምር፣ በእርስዎ ላይ ከፍ ያለ ሐሜት ያስከትልብዎታል። እኔም በችሎታዬ ተማምኜ እንዳልሠራ ደካማ ያደርገኛል። ስለዚህ ጌታዬን የምለምነው፣ በሒሳብም፣ በፈረንሣዊኛም፣ ፈተና እንዲሰጠኝና በውጤቱ መሠረት ጌታዬ እንዲወስኑ ነው » የሚል መልስ ሰጡ። ባለሥልጣኑ በጣም ተገረሙ። ይህ ሰው በተፈጥሮው ግትር -ሐቀኛ ወይም ደግሞ ጠማማ-ነገረኛ ሊሆን ይችላል። በማመልከቻው እንደገለጸው፣ ችሎታውና የሥራ ልምዱ በቂ ስለሆነ፣ ሥራውን ጀምር ሲባል፣ ካልተፈተንኩና ችሎታዬ ካልተረጋገጠ አልቀበልም የሚል ሥራ ፈላጊ፣ እስከዛሬ ታይቶ አይታወቅም ካሉ በኋላ፣ መቸስ ምን ይደረግ ? አመልካቹ በጠየቀው መሠረት ሙሴ ፋዋድ የተባለው ግብፃዊ የጉምሩክ ቀረጥ ባለሞያ፣ በሒሳቡም ሆነ በፈረንሣዊኛው ይፈትነውና ውጤቱን ያቅርብልኝ የሚል ትዕዛዝ ሰጡ።

መኰንን ሀብተወልድ ፊታቸው ኮስታራ፣ በጣም ከሲታ፣ አለባበሳቸው የጥንቱን ወግ የተከተለ ተፈሪ ሱሪና ኩታ ስለሆነ፣ ሙሴ ፋዋድ ገና ሲያያቸው ይኸ ሰው ያልሠለጠነ ነው ብሎ አልወደዳቸውም። አስፈላጊውን ፈተና ከመስጠቱ በፊት በቃል ጥያቄና መልስ ላይ፣ ሁለቱ ሰዎች ሊግባቡና ሊጣጣሙ አልቻሉም። ከብዙ ዓመታት በኋላ የዚህን ታሪክ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ለወንድሞቻቸው እንዳጫወቷቸው፣ ከሙሴ ፋዋድ ጋር ያደረጉት የንትርክ ውይይት እንደሚከተለው ነበር።

ሙሴ ፋዋድ፣ ምን ተምረሃል ?

አቶ መኰንን፣ በአሊያንስ ፍራንሴዝ ከሁለት ዓመት ተኩል ባላነሰ ጊዜ፣ ሒሳብና የፈረንሣዊኛ ቋንቋ አጥንቻለሁ።

ሙሴ ፋዋድ፣ እንግሊዝኛ ታውቃለህ ?

አቶ መኮንን፣ እንግሊዝኛ አላጠናሁም። ደግሞም ከውጭ አገር ቋንቋ ፈረንሣዊኛ ከታወቀ፤ የእንግሊዝኛ አስፈላጊነቱ አይታየኝም።

ሙሴ ፋዋድ፣ አስተያየትህ ጠባብ ነው። እንግሊዝኛ ማወቅ በጣም ጠቃሚ ነው። ለምሳሌ እኔ፣ እንግሊዝኛና ፈረንሣዊኛ አውቃለሁ።

አቶ መኮንን፣ ይስሙኝ ! ሙሴ ፋዋድ ! እርስዎ ግብፃዊ እኔ ኢትዮጵያዊ መሆኔን አይርሱት። እርስዎ እንግሊዝኛ ያወቁት አገርዎ የሚተዳደረው በእንግሊዞች ስለሆነ፣እንግሊዝኛ ማወቅ ለርስዎ ግዴታ ነው። ለእኔ ግን አይደለም።

ሙሴ ፋዋድ፣ አንተ ሰው ! እኔ እንደማይህ " ነገረኛ " ትመስለኛለህ። ይህ የጉምሩክ ሥራ ማከናወኛ ቢሮ ነው እንጂ የነገረተኞች ጉዳይ ማስፈጸሚያ አይደለም። ስለዚህ ለምን የፍርድ ቤቶች ጸሐፊ ለመሆን አትሞክርም ?

አቶ መኮንን፣ እኔ ነገረኛ አይደለሁም። ነገር የሚጉነጉኑት እርስዎ ነዎት። የፈረንሣዊኛና የሒሳብ ችሎታዬን ፈትነው ውጤቱን እንዲያቀርቡ የታዘዙትን ትተው፣ እንግሊዝኛ ለምን አታውቅም ? እያሉ ያስቸግሩኛል። ይህንንም የሚያደርጉት ለእኔ ፈተና ለመስጠት የፈረንሣዊኛ ችሎታዎ በቂ ስላልሆነ ደካማነትዎን ለመሸፈን ይመስለኛል። ስለዚህ፣ እንደገና ወደ ዋናው ባለሥልጣን ቢሮ ተመልሼ ችሎታ ያለው ሰው እንዲፈትነኝ አመለክታለሁ።

አቶ መኮንን እስከዚህ የተዳፈሩት፣ ከአንድ ወዳጃቸው እንደሰሙት፣ ሙሴ ፋዋድ ከእንግሊዞች ጋር ለብዙ ዘመን የሠራ በመሆኑ ችሎታው እንግሊዝኛ እንጂ፣ ፈረንሣዊኛው ደካማ ነው ይባላል። ፋዋድ ደግሞ መኮንንን በንቀት ስለተመለከታቸውና ችሎታቸውንም ለማንኳሰስ መፈለጉ ስለተሰማቸው፣ መኮንን ሀብተወልድ ሳይቀድመኝ ልቅደመው በማለት፣ ያንተ ፈረንሣዊኛ እኔን ለመፈተን በቂ የሚሆን አይመስለኝም፣ የሚል ተንኮል ጫሩበት። በዚህ ጊዜ ሙሴ ፋዋድ ይደነግጣል። ከዚህ ከነገረኛ ሰው ጋር በሰላም መገላገል ይሻላል ይልና፣ የመኮንን ፈረንሣዊኛ እስከምን ድረስ እንደሆነ መፈተኑን ትቶ፣ የአራቱን መደብ ሒሳቦች ብቻ በሩብ ሰዓት ውስጥ እንዲያጠናቅቁ ይጠይቃቸዋል።

መኮንን ሀብተወልድ ፈተናውን ተቀብለው በዐሥር ደቂቃ ውስጥ ሠርተው ትክክለኛውን ውጤት አቀረቡለት። ቀደም ሲል በአሩሲ የገበያ ቀረጥና የአሥራት ጸሐፊ በነበሩበት ዘመን፣ ከዚያም በኋላ ከሦስት ዓመት ተኩል ጀምሮ በፍልውሃ መግቢያ ገንዘብ ተቀባይነት ሲሠሩ፣ በጥሬ ባቄላ ቆጠራ የሒሳብ ሥራ ልምድ ስላላቸው፣ በአሊያንስ ፍራንሴዝ ያጠኑትን ዘመናዊውን የአራት መደብ የሒሳብ አሠራር ለማቀላጠፍ አልተቸገሩም።

ሙሴ ፋዋድ የሒሳቡን ውጤት ከተመለከተ በኋላ፣ ‹‹ …. ፈተናውን በሚገባ አልፈሃል። ለሒሳብ ክፍል ችሎታህ በቂ ስለሆነ፣ በቶሎ ሥራውን እንድትጀምር ለዋናው ባለሥልጣን ዛሬውኑ አቀርባለሁ። ….. ›› አላቸው።

መኰንን ይህ ውሳኔ ትክክል አይደለም የሚል ችግር መፍጠር ፈለጉ። « .... እኔ እንድፈተን ከዋናው ባለሥልጣን ትዕዛዙ የተላለፈልዎ ለሒሳብ ሥራ ብቻ ሳይሆን፣ የፈረንሣዊኛዬንም ችሎታ ነው። ስለዚህ፣ ፈተናው ሳይሟላ ሥራ መቀበል አልፈልግም .... » አሉት። እዚህ ላይ ግብፃዊው ፋዋድ ከመኰንን የበለጠ ተንኰለኛ ለመሆን መንገድ አገኙ። «ስማኝ ወንድሜ ! አንተ ያመለከትከው በፈረንሣዊኛ ለመሥራት ከሆነ በጣም ጥሩ ነው። እንዲያውም እንደአጋጣሚ የላጋር ጉምሩክ ባለሥልጣን የፈረንሣዊኛ ቋንቋ ተናጋሪዎች ከሆኑት ከልዩ ልዩ ለጋሲዮኖች ጋር ለሚጻጻፉት ኮሬስፖንዳንስ፣ የጸሐፊነትና የተርጓሚነት ሥራ ክፍት ቦታ አለን። ለዚህ ሥራ ያንተ ችሎታ በቂ ከሆነ ወዲያውኑ ትቀጠራለህ። ፈተናውንም አሁን እሰጥሃለሁ። ለጋሲዮኖች ከቀረጥ ነፃ ስለሚያስገቧቸው ዕቃዎች ጉዳይ፣ ባለፈው ሳምንት የጉምሩክ ባለሥልጣን በአማርኛ የሰጡትን አንድ ገጽ መምሪያ በግማሽ ሰዓት ወደ ፈረንሣዊኛ ተርጉመህ አቅርብልኝ ..... » አላቸው። አሁን ደግሞ መኰንን ሀብተወልድ በተራቸው ደነገጡ። እሳቸው ፈረንሣዊኛዬ በፈተና ካልታየልኝ ብለው የተሟገቱት፣ ከየለጋሲዮኖቹና በኢትዮጵያ እየነገዱ ከሚኖሩት የውጭ አገር ሰዎች ጋር አንዳንድ የዕለት ጉዳዮችን ለማስፈጸም የሚያስችል ችሎታ አለኝ ለማለት ነው እንጂ፣ መሠረታዊ የሆኑ ዶክመንቶችን ለመተርጐም አልነበረም። እንግዲያውስ ምን ይሻላል ? « .... እኔ በፈረንሣዊኛ ቋንቋ የትርጉም ሥራ ችሎታ አለኝ ብዬ አላመለከትኩም ..... » ብለው መልስ መስጠት ግዴታ ሆነባቸው።

ሙሴ ፋዋድ ፈረስ ላይ ወጣ። የሥራ አመልካቹን ደካማ ጐን አገኘሁ ብሎ ደስ አለው። « ..... ታዲያ፣ ያለ-አቅምህ ያለ ችሎታህ በፈረንሣዊኛ ከእኔ ጋር ለመወዳደር ምን አንጠራራህ ? .... » አላቸው። አሁንም አቶ መኰንን መልሳቸውን ማለስለስ አልፈለጉም። « ..... ከአቅሜ በላይ የሆነ ነገር አልተናገርኩም። የሰጡኝ የትርጉም ፈተና እርስዎ ራስዎ መሥራት የማይችሉትን ነው። ይህንንም ያደረጉት ሆነ ብለው ሊጉዱኝ ስለፈለጉ ነው። ለሁለት ዓመት ተኩል ያጠናሁት ፈረንሣዊኛ ለአንዳንድ ሥራ ይረዳ እንደሆነ ይታይልኝ ብዬ መጠየቄ፣ ለከፍተኛ የትርጉም ሥራ አለመሆኑን ደህና አድርገው ያውቁታል። ነገር ግን ዓላማዎ የኔን ዕድል ማሰናከል ስለሆነ፣ ከበላይ ባለሥልጣን የደረስዎትን ትዕዛዝ በቅን መንፈስ መፈጸም አልፈለጉም። ስለዚህ፣ ያለኝ ምርጫ እንደገና ወደ ባለሥልጣኑ ተመልሼ ኃዘኔን መግለጽ ብቻ ነው .... » አሉት። አሁን ደግሞ ሙሴ ፋዋድ ትንሽ ረገብ አለ። « .... ለእኔ እናንተ ወንድሞቼ ኢትዮጵያውያኖች በጣም የምትገርሙኝ፣ ሁልጊዜ በራሳችሁ በጣም ስለምትተማመኑ፣ የሰው ምክር አልሰማ ማለታችሁ ነው። ከሚያስፈልግ በላይ ራስን ሁልጊዜ ከፍ ማድረግ ከጥቅሙ ጉዳቱ እንደሚያመዝን ማወቅ አለባችሁ። .... አሁን ሁሉንም ነገር እንተወውና ወደፊት አንተና እኔ አብረን የመሥራት ዕድል ስለሚኖረን፣ በመካከላችን ያለውን ንትርክ ወደ ሰላም እንለውጠው። « .... አንተ ሥራ ፈላጊ ሆነህ ነው እኛ ዘንድ የመጣኸው። እኛ ደግሞ ለሒሳብ ሠራተኛነት ችሎታህ በቂ ሆኖ ስለአገኘነው፣ ለሥራው ተዘጋጅ ብለንሃል። እኔም ዛሬውኑ ያንተን ጉዳይ ለአለቃዬ አቅርቤ አስፈጽማለሁ .... » ካለ በኋላ፣ ከወንበሩ ብድግ ብሎ እጃቸውን ጨበጣቸው።

አቶ መኰንን ለሙሴ ፋዋድ ምስጋናቸውን ካቀረቡ በኋላ፣ ተሰናብተው ከመውጣታቸው በፊት፣ አንድ አስተያየት ለመግለጽ እንዲፈቀድላቸው ጠየቁ። ፋዋድም ተናገር አዳምጥሀለሁ አላቸው። « .... ወደፊት በእግዚአብሔር ፈቃድ አብረን የመሥራት ዕድል ይኖረናል ብዬ ተስፋ አደርጋለሁ። ለዚህም ከዛሬ ጀምሮ

ልንጠቀምበት የሚያስፈልገን አንድ ዋና ቁም ነገር አለ። የርስዎና የእኔ ግንኙነት ወደፊት የሚመሠረተው፣ ምንም እንኳ በአለቃና ጭፍራ ደረጃ ቢሆንም፣ በየጉዳዩ ላይ የምናስበውን ሁሉ ተገላልጠን በሐቅ ብንነጋገር፣ ለሥራችንም ሆነ ለግላችን በጣም ይጠቅመናል ብዬ አስባለሁ። በዚህ ዓይነት መንፈስ የተመራን እንደሆነ፣ በመካከላችን በሚኖረን የሥራ ግንኙነት ከመግባባትና ከመተማመን በስተቀር፣ ምንም ዓይነት መቃቃር ወይም አለመጣጣም ሊደርስብን አይችልም። ይህን ሐሳብ እርስዎ የሚቀበሉት ከሆነ፣ ቀደም ሲል ስለ እኛ ኢትዮጵያውያኖች ስለተናገሩት መሠረታዊ ጉዳይ እኔም ከልቤ የማስበውን ሳይውል ሳያድር ዛሬውኑ ብገልጽልዎ የተገባ መስሎ ታይቶኛል። ወንድሞችዎ ኢትዮጵያውያኖች በሚያሳዩት የራስ መተማመን ምን ያህል እንዳስገረምዎና፣ ይህም ምንም ዓይነት ጥቅም እንደሌለው አስረድተውኛል። በዚህ ጉዳይ ላይ እኔ የምሰጠውን አስተያየት ወገኔ የኢትዮጵያ ሕዝብ በሙሉ የሚያምንበት መሆኑን አረጋግጥልዎታለሁ። የኛ የኢትዮጵያውያኖች በራስ መተማመን ጥንትም የነበረ፣ ዛሬም ያለ፣ ነገም የሚቀጥል ለመቸውም የማይለወጥ ጠባይ መሆኑን እንዲገነዘቡት እፈልጋለሁ። እርስዎም ጉዳዩን ከመሠረቱ ቢመለከቱት፣ ይኸ ለብዙ ሺህ ዓመታት ከጠላቶቹ ጋር እየተዋጋ መከራን እየተቀበለና እያሸነፈ፣ ነፃነቱን አሳስነካም ብሎ ታሪኩንና ባህሉን ጠብቆ የሚኖር ሕዝብ፣ በራሱ ካልተማመነ በማን ሊተማመን የሚችል ይመስልዎታል ? ... እንደሚያውቁት የሌሎች አገሮች ሕዝቦች፣ ሳይወዱ በግድ የውጭ ገዥዎች ጫና ወድቆባቸው ነፃነታውን አጥተው ስለሚኖሩ፣ የራስ መተማመን ዕድል ሊኖራቸው አይችልም። እኔ እንደዚህ ስናገር፣ ከካህን ቤተሰብ የተወለድኩና ዕድገቴም በቤተክርስቲያን ሥርዓት በመሆኑ፣ ነገር የሚወድ ነገረኛ ነው ብለው ሳይገምቱኝ አይቀሩም። በውነቱ ነገር ለማብዛት ወይም ለማንዛዛት ፈላጊ አይደለሁም። ነገር ግን በማናቸውም ጉዳይ አንድ ነገር አዕምሮዬ ላይ ከተቀረፀ፣ ያንን አውጥቼ ሳልናገር ውዬ ማደር አልችልም። ይኸ የተፈጥሮ ጠባዬ ነው .... » ብለውት፣ ከቢሮው ወጡ።

ፋዋድ አሁንም በአቶ መኰንን ንግግር በጣም ተገረመ። « ... ይኸ ሰው ፈረንሣዊኛ አውቃለሁ ይላል እንጂ፣ ደህና አድርጐ የሚያውቀው ነገር ነው። ያለ ጥርጥር ከጨቅጫቃነቱም በላይ ተንከለኛም ሳይሆን አይቀርም። እርግጥ! በሒሳብ ችሎታው ጥሩ ውጤት አሳይቷል። ሆኖም የጠባዩ ነገር ስለአሠጋኝ፣ ጌታዬ የመሰለዎትን ይወስኑ .... » ሲል ፋዋድ ራፖሩን ለበላይ አቀረበ። የላጋር ጉምሩክ ዋናው ባለሥልጣን ምንም እንኳ እሳቸውም ስለመኰንን ሀብተወልድ በመጀመሪያው ቀን ያደረባቸው ስሜት ከሙሴ ፋዋድ አስተያየት ጋር የተቀራረበ ቢሆንም፣ « .... ሰውየው የሒሳብ ችሎታው በቂ ስለሆነ፣ የሒሳብ ሹሙ ረዳት ሆኖ እንዲሠራ ቢሮ ይረከብና ይታይ ! ..... » የሚል ውሳኔ ሰጡ።

# መኰንን ሀብተወልድ
# በላጋር ጉምሩክ ሒሳብ ክፍል

የሒሳብ ሹሙ ረዳት ተብለው ቢሮ በያዙ በወሩ፣ መኰንን ሀብተወልድ ከበላይ አለቆቻቸውና በተለይም ከዋናው የጉምሩኩ ባለሥልጣን ጋር መልካም መግባባትና ግንኙነት ፈጠሩ።

ከጉምሩክ ቀረጥ በየዕለቱ ለመንግሥት የሚገኘውን ገቢ በአንድ መልክ፣ ከዚያ ደግሞ በየሳምንቱ የተሰበሰቡትን ገቢዎች በሰንጠረዥ እየተከሉ፣ የሚያቀርቡት የሒሳብ መግለጫና ማጠቃለያ ስታቲስቲክ፣ ዋናውን ባለሥልጣን ብቻ ሳይሆን፣ አማካሪና የቀረጥ ጉዳይ ኤክስፐርት የተባለውን ሙሴ ፉዋድን ጭምር አስደሰተ። እንደዚያ ጨቅጫቃና ነገረኛ ሳይሆኑ አይቀሩም ተብለው የተገመቱት ሰው፣ ኃላፊነት ተቀብለው ቢሮ ሲይዙ፣ የተሰጣቸውን የሒሳብ ሥራ በትክክል ከመሥራትና ከሥራ ጓደኞቻቸውም ጋር በቅን መንፈስ ከመተባበር በስተቀር፣ ሙሴ ፉዋድ እንደሠጋው የአስቸጋሪነትና የነገረኛነት ጠባይ ሳይታይባቸው ቀረ። ይሁን እንጂ፣ የመኰንን ሀብተወልድ የተፈጥሮ ጠባይ ከሥራ ጓደኞቻቸውና ከአለቆቻቸው ጋር ለመግባባት ቅድሚያ የሚሰጡ መስለው ቢታዩም፣ የአገርንና የመንግሥትን ጥቅም በሚመለከት ጉዳይ፣ የሚያስቡትንና የሚያምኑበትን በድፍረት ከመግለጽ የሚቆጠቡ ሆነው አልተገኙም።

አንድ ጊዜ፣ የጉምሩኩ ዋና ባለሥልጣን በሳምንት አንድ ቀን የየክፍሉን ኃላፊዎች እየሰበሰቡ፣ ስለሥራው አመራር በሚነጋገሩበት ዕለት፣ የሒሳብ ሹሙ በሕመም ቀርተው ስለነበረ፣ መኰንን ሀብተወልድ እንደተጠባባቂ ሹም ተቆጥረው፣ በስብሰባው ላይ እንዲካፈሉ ተደረገ። የዕለቱ የስብሰባው አጀንዳ፣ ከጉምሩክ ቁጥጥር እያመለጡ በሠርጐ ገብ (ኮንትረባንድ) አገር ውስጥ የሚገቡት የንግድ ዕቃዎች በየጊዜው እየጨመሩ በመሄዳቸው፣ መከላከያውን በምን አኳኋን ለማጠንከር ስለሚቻልበት ዘዴ ለመነጋገር ነበር።

በዚህ ስብሰባ ላይ ለመጀመሪያ ጊዜ ተካፋይ የሆኑት መኰንን ሀብተወልድ፣ በእኔ በኩል የማቀርበው አስተያየት አለኝ ብለው፣ የሊቀመንበሩን ፈቃድ ጠየቁ። በዚህ ጊዜ፣ ዋና አማካሪና የቀረጥ አሰባሰብ ኤክስፐርት የተባለው ሙሴ ፉዋድ፣ ይኸ ሰው ምን ሊናገር ይሆን? በማለት ዓይኑን ተከለባቸው። ሌሎቹም በስብሰባው ላይ ተካፋይ የሆኑት ሹማምንቶች አለቃው ስለሌለ የጉባኤውን ውጤት እንዲያዳምጥ የተጠራ አንድ ረዳት ሠራተኛ፣ ከየክፍሉ ኃላፊዎች እኩል ለመናገር እንዴት ይፈቀድለታል? በማለት ሊቀመንበሩን አተኩረው ተመለከቱ። የስብሰባው መሪ የሆኑት ዋናው ባለሥልጣን ግን፣ ከረዳት ሠራተኛው ለመናገር የቀረበላቸውን ጥያቄ ስለፈቀዱ፣ መኰንን ሀብተወልድ ያለ አንዳች ይሉኝታና ሥጋት የሚከተሉትን ሁለት አስተያየቶች አቀረቡ።

## 1ኛ/ ስለ ኮንትሮባንድ፣

በዚህ መሥሪያ ቤት ትናንት የተቀጠርኩ አዲስ ሠራተኛ በመሆኔ፣ በዚህ በከፍተኛ ስብሰባ ላይ እኔም ሐሳብ አለኝ ብዬ ለመናገር ፈቃድ በመጠየቄ እንደተገረማችሁ ተሰምቶኛል። እኔ ለመናገር ፈቃድ የጠየቅኩት፣ እንዲሁ መያዣና መጨበጫ የሌለው ከአየር ላይ የተቃረመ ሐሳብ አምጥቼ ጊዜያችሁን ለማባከን

አይደለም። ባለኝ አቅሜ አጥንቼ የተረዳሁትንና ለመሥሪያ ቤቱም ይጠቅማል ብዬ ያመንኩበትን ስለሆነ፣ ፈቃዳችሁንና ትዕግሥታችሁን እለምናለሁ።

ሕግ እየተጣሰ በአገራችን ውስጥ የሚሠራጩት የንግድ ዕቃዎች በየዓመቱ እየጨመሩ ሄዱ እንጂ አልቀነሱም። ይህን ሕገ ወጥ ሥራ ለመከላከል፣ በየጊዜው ስብሰባ እየተደረገ ሲጠና እንደቆየ እስከዛሬ ከተያዙት ቃለ ጉባኤዎች ለመረዳት ችያለሁ። ይሁን እንጂ፣ እስከዛሬ በተደረጉት ስብሰባዎች ሁሉ ለችግሩ አንድ ከፍተኛ እርምጃ መውሰድ ማስፈለጉን ከመወያየት በስተቀር፣ ምን ማድረግ እንደሚገባ የተደረገ ቁርጥ ውሳኔ የለም። ስለዚህ፣ ለችግሩ በሽታው የት ላይ እንደሆነና ማጥፊያውም ምን መሆን እንዳለበት በቶሎ ካልተወሰነ፣ በየጊዜው በስብሰባ ላይ ውይይት መደረጉ አንዳች ጥቅም ሊሰጥ አይችልም። እኔም ዛሬ የማስበውን ልናገር ብዬ ፈቃድ የጠየቅኩት፣ ለገጠመን ችግር መፍትሔ ይሆናል ብዬ ያመንኩበትን ለማቅረብ ነው እንጂ፣ በኮንትረባንድ ሕገ ወጥ ሥራ ምክንያት በመንግሥቱ ገቢ ላይ ስለአስከተለው ጉዳት ኃዘኔን ለመግለጥ አይደለም። ስለዚህ በእኔ አስተያየት ወደ አገራችን በኮንትረባንድ የሚገቡትን የንግድ ዕቃዎች መያዝና ሕገወጦቹን ለቅጣት ማቅረብ ኃላፊነቱን መውሰድ ያለባቸው፣ ከምስለኔ እስከ ወረዳ፣ ከዚያም እስከ አውራጃ ግዛት ያሉት አገረ ገዥዎች ናቸው። ከትንንሾቹ እስከ ታላላቆቹ ድረስ ያሉት አገረ ገዥዎች፣ ለመንግሥት ማሰብና የመንግሥትን ጥቅም መጠበቅ፣ ግዴታቸው መሆኑን ማወቅ ብቻ ሳይሆን፣ ከልባቸው ማመን ይኖርባቸዋል። አንድ ሰው በትዕዛዝ ከሚሠራው ይልቅ ከልቡ አምኖበት የሚያደርገው ጥረት የበለጠ ውጤት ያመርታል። መንግሥት ለሕዝብ እድገትና መልካም አስተዳደር የሚገባውን መሥራት የሚችለው፣ የአገር ነፃነትን ከውጭ ጠላት መከላከል የሚችለው፣ ገቢው ሲዳብርለትና አቅም ሲያገኝ ነው። ነገር ግን መንግሥት የገቢው ቋቱ ከተራቆተበት፣ ደካማ ይሆናል። አስተዳደር ይበላሻል። ፍርድ ይዛባል። ፀጥታ ይታወካል። ይህ ሁሉ ከደረሰ ደግሞ፣ ችግሩ ማንን ነው የሚያጠቃው? ተብሎ ቢጠየቅ፣ ያው ጠላት የማይተኛለት፣ መከራና ፈተና የማይለየው የፈረደበት የኢትዮጵያን ሕዝብ መሆኑን አንስተውም። ስለዚህ፣ ቀደም ብዬ እንዳመለከትኩት፣ የኮንትረባንድ ሕገወጦችን ለማጥፋት ዋናዎቹ ኃላፊዎች አገረገዥዎች መሆን ስለሚገባቸው፣ ጉዳዩ በገንዘብና በአገር ግዛት ሚኒስትሮች ተጠንቶ፣ በልዑል አልጋወራሽ ተፈሪ መኩንን እንዲወሰንና አዋጅ ወጥቶ በሥራ ላይ እንዲውል ያስፈልጋል። በበኩሌ ከዚህ የተሻለ መፍትሔ ይኖራል ብዬ አላስብም።

## 2ኛ/ ስለ ዲፕሎማቶች የቀረጥ ነፃ መብት

እኔ ይህን ከባድ ጉዳይ ያነሣሁት፣ በዛሬው ስብሰባ ላይ ንግግር እንዲደረግበት አጀንዳ ያልተያዘለት መሆኑን ሳላውቅ ቀርቼ አይደለም። ነገር ግን ጉዳዩ አንድ አስቸኳይ ውሳኔ እንዲሰጥበት አስፈላጊነቱን በማመን፣ ደፍሬ ጣልቃ በማስገባቴ ይቅርታ እለምናለሁ።

በአዲስ አበባ ነዋሪ የሆኑት የልዩ ልዩ አገሮች ለጋሲዮኖችና ቆንስሎች በየጊዜው ከፈረንጅ አገር ከቀረጥ ነፃ የሚያስመጧቸው ዕቃዎች ወሰን ወይም ገደብ አይታይባቸውም። ቀጥሎ ደግሞ ዲፕሎማቶቹ በብዛት የሚያስመጧቸው ዕቃዎች ምንና ምን መሆናቸውን መንግሥት ለማወቅ የሚችልበት መንገድ የለውም። ይህንን ሁሉ ከተመለከትኩ በኋላ፣ ቀድሞ ለፍልውሃ መጠመቂያ መግቢያ ገንዘብ ተቀባይ ሆኜ በምሠራበት ጊዜ፣ የተዋወቅኳቸውንና በወዳጅነት የቀረብኳቸውን

አንዳንድ የፈረንጅ አገር ቆንስሎች፣ በእነሱ አገር ለዲፕሎማቶች ስለሚሰጠው የቀረጥ ነፃ መብት፣ አሠራሩ በምን አኳኋን እንደሆነ እንዲነግሩኝ ጠይቂያቸው ያገኘሁትን እንደሚከተለው አቀርባለሁ።

ሀ/ የአንድ አገር ሌጋሲዮን ወይም ቆንስል ከውጭ አገር ለማስመጣት የሚፈልጋቸውን ዕቃዎች፣ የእያንዳንዳቸውን ዓይነትና ዋጋቸውን ዝርዝር የቀረጥ ነፃ ፈቃድ እንዲሰጠው ለውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ያመለክታል።

ለ/ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ደግሞ በበኩሉ ከውጭ ለማስመጣት የተጠየቁት ዕቃዎች በደንቡ መሠረት ለሌጋሲዮኑ ወይም ለቆንስሉ አገልግሎት የሚውሉ መሆናቸውን ካረጋገጠ በኋላ፣ አስፈላጊውን "የማስመጫ ፈቃድ" * ሲሰጥ ለጉምሩክ ዋና መሥሪያ ቤት በግልባጭ ያስታውቃል።

ሐ/ ከውጭ አገር ዕቃዎቹ መጥተው ከዋናው ከተማ ጣቢያ ሲደርሱ፣ ሌጋሲዮኑ ወይም ቆንስሉ፣ መጀመሪያ በጠየቀው የማስመጫ ፈቃድ መሠረት፣ " ዴክለራሲዮን " (መግለጫ) ፎርም ሞልቶ ለጉምሩክ ያቀርባል። በዚህ ጊዜ የጉምሩክ ባለሥልጣን ከውጭ ለማስመጣት የተሰጠውን ፈቃድና ከዋናው ከተማ የደረሱትን ዕቃዎች ዝርዝር አመሳክሮ ትክክል መሆናቸውን ካረጋገጠ በኋላ፣ የይለፍ ፈቃድ ይሰጥና ባለቤቱ ዕቃዎቹን ተረክቦ ይወስዳል።

እስከዛሬ ድረስ ያለው የኛ አሠራር ግን፣ ሌጋሲዮኖቹንና ቆንስሎቹን ከሚገባው በላይ የሚያቃብጥ፣ እንዲያውም ትዕዛዝ ተቀባይ መስሎ የሚታይ ነው። አንድ ሌጋሲዮን ወይም ቆንስል ከውጭ አገር ዕቃዎች ለማስመጣት በቅድሚያ ፈቃድ አይጠይቅም። ዕቃዎቹ አዲስ አበባ ከደረሱ በኋላ፣ ይህን ያህል "ጥቅል" የሆኑት ዕቃዎች የኔ ስለሆኑ፣ ከጉምሩክ በአስቸኳይ እንዲለቀቁልኝ ብሎ ሌጋሲዮኑ ወይም ቆንስሉ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ሲጽፍ፣ እኛም ትዕዛዙን ተቀብለን በቶሎ የይለፍ ፈቃድ እንሰጥና እናስረክበዋለን።

እንግዲህ ! እንደምታዩት፣ በዚህ አሠራር የኢትዮጵያ መንግሥት ክብርና ሥልጣን አልተነካም ወይ? ... የክብር መነካት ጉዳይ ብቻ ሳይሆን ይህን የመሰለው ቸርነት ጉዳትና አደጋ አያስከትልም ወይ? ... **እያንዳንዱ ሌጋሲዮን ወይም ቆንስል እንደፈለገውና እንደአሰኘው የሚያስመጣቸው ዕቃዎች ምንድን ናቸው ?** እነዚህ ዝርዝር ዓይነታቸው የማይታወቁ፣ በብረት ቦንዳ እየታሠሩና እየታሸጉ ከውጭ የሚመጡት ነገሮች፣ በአገር ውስጥ ሽብር ለማስነሣት ለከፋዎችና ለተንኮለኞች የሚሠራጩ የጦር መሣሪያዎች ሊሆኑ አይችሉም ወይ ? በምን እናውቃለን ? ስለዚህ፣ እኔ " አደገኛ " ነው ብዬ የምገምተው ይህ ጉዳይ በጥንቃቄ ተጠንቶ አንድ አስቸኳይ እርምጃ እንዲወሰድበት እያሳሰብኩ፣ በሁለተኛ ደረጃ ይኸው አሠራራችን ጉዳት ያስከትላል ብዬ የተጨነኩበትን ለማስረዳት እሞክራለሁ።

ቀደም ሲል እንደተናገርኩት፣ እነዚህ በብረት ቦንዳ እየታሸጉ በሌጋሲዮኖቹ ስም ወደ አገራችን የሚገቡት ዕቃዎች እኔ እንደምጠረጥረው የጦር መሣሪያዎች

---

* Import Permit

ካልሆኑ፣ ሌላ ምን ሊሆኑ ይችላሉ? ብዬ ሳጠና ከልዩ ልዩ የቤት ዕቃዎች እንደ ወንበሮችና ጠረጴዛዎች ከመሳሰሉት ሌላ፣ እንደ ሰዓቶች፣ እንደ ወርቅና እንደ አልማዝ የመሳሰሉትን ልዩ ልዩ ጌጣጌጦች፣ በብዛት እያስመጡ በስውር ለባለጸጎች በመሸጥ የሚጠቀሙበት አይሆንም ወይ? የሚል ጥርጣሬ አድሮብኛል። ጥርጣሬም የማበዛው፣ እኛ ኢትዮጵያውያን በማናቸውም ረገድ የውጭ አገር ሰዎችን ከመጠርጠር ችላ ማለት የለብንም የሚል እምነት ስላለኝ ነው።

እንግዲህ ! ለአገራችን ደህንነትና ለአገራችን ጥቅም ሲባል በጉምሩክ አሠራራችን ሌላው ዓለም የሚጠቀምበትን መንገድ ብንከተል፣ በኢትዮጵያ ነዋሪዎች የሆኑትን የውጭ አገሮች ሊጋሲዮኖችና ቆንስሎች መብት የሚነካ ወይም የሚያስቀይም ስለማይሆን፣ ጊዜ ሳናባክን አንድ የተቆረጠ ውሳኔ እንድናደርግ ሐሳቤን በትሕትና አቀርባለሁ።

ከተሰበሰቡት የክፍል ሹማምንቶች መካከል፣ በዚህ በመኩንን ሀብተወልድ ንግግር የተደሰተ አልነበረም። አንድ ተራ ሠራተኛ የጉምሩኩን አሠራር መንቀፍ ብቻ ሳይሆን መሻሻል የሚያስፈልገው እኔ በማቀርበው ሐሳብ ነው ብሎ እስከዚህ የሚዳፈረው በምን ምክንያት ነው? እያሉ ሹማምንቶቹ እርስ በርሳቸው ሲንሾካሾኩ መኩንን ሀብተወልድ አተኩረው ተመልክተዋል። ሆኖም ሹክሹክታው "ተራ" በተባለው ሠራተኛ ላይ ያደረሰው ጉዳት የለም። የስብሰባው መሪ የጉምሩኩ ዲሬክተር አቶ መኩንን በተናገረውና ባቀረበው ሐሳብ ላይ ጥያቄና አስተያየት ያላችሁ በየተራ ለመናገር እጃችሁን አውጡ ! አሉ። ሹማምንቶቹ በሙሉ ፊታቸውን አኮራምተው ዝም ሲሉ፣ የመሥሪያ ቤቱ አማካሪና ኤክስፐርት የተባለው ሙሴ ፉዋድ ብቻ ጥያቄ አቀረበ።

<u>ፉዋድ</u>፣ -- በውጭ አገሮች ያሉት የጉምሩኮች አሠራር አሁን ባስረዳኸን መሠረት መሆኑን የነገረህ ቆንስል ማን መሆኑን ልትገልጽልን ትችላለህ?

<u>መ.ሀ</u>፣ -- ይህንን የሌሎቹን አገሮች የጉምሩኮች አሠራር ያስጠናኝ ሰው፣ ከእኔ ጋር ካለው ወዳጅነት ይልቅ፣ ኢትዮጵያን የሚወድና ለኢትዮጵያ ተቆርቋሪ ሳይሆን አይቀርም እላለሁ። ሆኖም ስሙን በስብሰባ ላይ መግለጽ ተገቢ አይመስለኝም። የጉምሩኩ ዲሬክተራችን ከጠየቁኝ ግን፣ በተለይ ልነግራቸው እችላለሁ።

<u>ፉዋድ</u>፣ -- ታዲያ በምሥጢር በተገኘ መረጃ ላይ ተመሥርተን እንዴት አሠራራችንን መለወጥ እንችላለን? አንተ የነገርከን ሁሉ ትክክል መሆኑን የምናረጋግጥበት ሌላ መረጃ ያስፈልገናል።

<u>መ.ሀ</u>፣ -- እኔ ባቀረብኩት መረጃ ላይ ተመሥርተን አሠራራችንን ለመለወጥ እንቸገራለን ከተባለ፣ አዲስ አበባ ያሉትን ሊጋሲዮኖችና ቆንስሎች ስለ ዲኘሎማቶች የቀረጥ ነፃ መብት ጉዳይ የየአገራችሁ ሕግናአሠራር እንዴት እንደሆነ ዶክመንት ስጡን ብለን በውጭ

ጉዳይ ሚኒስቴር በኩል በደብዳቤ ብንጠይቃቸው፣ የምንፈልገውን እናገኛለን።

ፉዋድ፣ -- ለጋሲዮኖቹ ለተጠየቁት መልስ አንሰጥም ብለው ዝም ካሉን ምን ማድረግ እንችላለን ? ...

መ.ሀ፣ -- መጀመሪያ ፣ ለጋሲዮኖቹ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር በጽሑፍ የሚጠይቃቸውን ጉዳይ መልስ አንሰጥም ማለት አይችሉም። እርግጥ ! የኢትዮጵያ መንግሥት ይህን ጥያቄ ያቀረበው፣ የኛን አገር አሠራር እከተላለሁ ብሎ ቁጥጥሩን ያጠነክርብን ይሆናል ብለው በመሥጋት ፣ በቶሎ መልስ ላለመስጠት ጊዜ ይፈጁ ይሆናል። ይሁን እንጂ ፣ የተጠየቁትን ካልመለሱ፣ ወይም ምክንያት እየፈጠሩ ጊዜ ከፈጁ፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴራችን በቀጥታ ለየአገሩ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ጽፎ፣ ዶክማውን* በፍጥነት ማግኘት ይችላል።

ፉዋድ፣ -- በዚህ ሐሳብ እስማማለሁ ። ሆኖም አሁን ያለንን አሠራር የምንለውጠው፣ የሌሎቹ አገሮች የጉምሩክ ሕግና አሠራር እንዴት እንደሆነ የሚገልጹት ዶክማዎች ከደረሱን በኋላ ነው።

ሙሴ ፉዋድ የምፈልጋቸውን መልሶች አግኝቻለሁ ካለ በኋላ፣ አቶ አገዘ በሱፈቃድ የተባሉት የጉምሩኩ የቀረጥ ክፍል ሹም፣ ለመኰንን ሀብተወልድ አንድ በተንኮል የተለወሰ አስፈላጊም ያልነበረ ጥያቄ አቀረቡ።

አቶ አገዘ፣ ቅድም ስትናገር፣ የፍልውሃ መግቢያ ገንዘብ ተቀባይ ሆነህ በምትሠራበት ጊዜ፣ ከአንዳንድ ቆንስሎች ጋር ወዳጅነት አፍርቼ፣ አሁንም ለሥራዬ ያቀረብኩትን ሐሳብ የረዱኝ እነሱ ናቸው ብለሃል። ይህን የመሰለ ወዳጅነት ለመጠቀም የቻልከው በአንተ በኩል ምን እርዳታ ብታደርግላቸው ነው ? ... መቸም ከፈረንጆች ጋር ወዳጅነት በደረቁ አይሆንም።

መ.ሀ፣ ወዳጅነትን ለማፍራት ያሉት መንገዶች ብዙዎች ናቸው። እርስዎ እንደሚያስቡት ወዳጅነት ሁልጊዜ ከጥቅም ጋር የተሳሰረ ወይም በገንዘብ የሚገዛ መሆን የለበትም። የፍል ውሃ መግቢያ ገንዘብ ተቀባይ የሆነ ሰው ደግሞ ዋጋው ተወስኖ በታተመ ደረሰኝ የሚሠራ ነው እንጂ፣ እንደ ጉምሩክ ቀረጥ ኃላፊ ክፍያውን በአስተያየት ከፍና ዝቅ የማድረግ ሥልጣን የለውም። በዚህም ምክንያት የፍልውሃ ገንዘብ ተቀባይ በሥራው የተለየ ጥቅም ያገኝበታል ወይም ደግሞ ወዳጅ ይገዛበታል የሚል ሐሜታ ሊደርስበት አይችልም። እኔ ፍልውሃ በምሠራበት ጊዜ ከአንዳንድ ቆንስሎች ጋር ወዳጅ የሆንኩት፣ ፍልውሃ ለመጠመቅ በመጡ ቁጥር መልካም አቀባበል ስለማደርግላቸውና

---

* ሰነድ

በዚቹም አሲያንስ ፍራንሲ ባጠናኂት የፈረንሣዊኛ ቋንቋ ስለአየሩም ስለንፋሱም ስለማነጋገራቸው ነው እንጂ፣ ከእኔ የተለየ ጥቅም ስለሚያገኙ አይደለም።

በአቶ መኰንን መልስ አሰጣጥ በስብሰባው ላይ የነበሩት ሁሉ (የጉምሩኩ ዲሬክተር ሳይቀሩ) አንገታቸውን አቀርቅረው በሣቅ ሲንፈራፈሩ፣ አቶ አገዘ ከማፈራቸው ብዛት ወንበራቸውን ለቅቀው ወደ ውጭ ወጡ። አቶ አገዘ በሥራቸው ላይ ጉቦ እንደሚቀበሉና የታላላቆቹ ባለሥልጣኖችም ድጋፍ አላቸው ስለሚባል፣ ሰው ሁሉ ይፈራቸዋል። መኰንን ሀብተወልድ ግን፣ አቶ አገዘ ራሳቸው የጫሩት እሳት መልሶ እንዲፈጃቸው በማድረጋቸው ሁሉም ተደሰቱ። ድሮስ ቢሆን ከደብተራ ልጅ ጋር የነገር ሙግት መግጠም ለምን አስፈለገ? እየተባለ ተተቸ።

ከዚህ በላይ እንደታየው ከአቶ አገዘ ቀጥሎ ሌላ ጥያቄ የሚያቀርብ ወይም አስተያየት የሚሰጥ ሰው ቢጠየቅ፣ ሁሉም ፀጥ አለ። ከዚህ በኋላ የመናገሩ ተራ የሊቀመንበሩ ሆነ።

## ይገርማል ! አሉ-ሊቀመንበር !

ይኸ ሰው ያቀረበልን ሐሳብ ለዲፕሎማቶቹ ስለሚደረገው የቀረጥ ነፃ መብት አሠራር ብቻ አልነበረም። የዛሬው ስብሰባችን ዋና ዓላማ በሆነው ስለ ኮንትሮባንድ መከላከያ ጉዳይ ጠቃሚ የሆነ ሐሳብ ሰጥቶን ነበር። ለዚህ ትልቅ ጉዳይ እንዳችሁም ጥያቄ ማቅረብ ወይም አስተያየት መስጠት ባለመፈለጋችሁ ወይም ችላ ብላችሁት በማለፋችሁ እጅግ አድርጌ አዝኛለሁ። ሆኖም በእኔ በኩል ጠቃሚ የሆኑትን ሁሉ በማስታወሻዬ መዝግቤ ለስብሰባችን የማጠቃለያ ሐሳብ እሰጣለሁ።

ስማ ! አቶ መኰንን ! ማንም ሳያዝህ፣ ማንም ሳይጠይቅህ፣ ከራስህ አመንጭተህ፣ ባቀረብክልን ሁለት ዋና ዋና ሐሳቦች ላይ የሚከተለውን ውሳኔ እሰጣለሁ።

አንደኛ/ በአገራችን በኮንትሮባንድ የሚሠራጨውን ሕገወጥ ንግድ ለማጥፋት፣ አንተ እንዳልከው አገረ ገዥዎች ሥራዬ ብለው ከተከታተሉት ፣ ችግሩ እንደሚወገድ እኔም አምንበታለሁ። ይህንንም ለማስፈጸም፣ የገንዘብና የአገር ግዛት ሚኒስትሮች አጥንተውና ተስማምተው በልዑል አልጋወራሽ መወሰን አለበት ያልከው ጥሩ ሐሳብ ነው። ይህን ያቀረብከውን ሐሳብ በዋናው የጉምሩክ መሥሪያ ቤት በኩል ለሚኒስትሮቹ እንዲተላለፍላቸውና እንዲነጋገሩበት፣ አስፈላጊውን ማስታወሻ አንተ አዘጋጅተህ በቶሎ ስጠኝ።

ሁለተኛ/ ለጋሲዮኖችና ቆንስሎች ከውጭ አገር ስለሚያስመጧቸው ዕቃዎች ያደረግከው ክትትልና ጥናት የሚደነቅ ነው። ከውጭ አገር በብዙ ገንዘብ ቀጥረን ያመጣናቸው አማካሪዎቻችን ያላሰቡበትንና ያላወቁትን አንተ ፈልፍለህ ደረስክበት። ይህንንም ያደረግከው ለአገርህ ባለህ ፍቅርና ለመንግሥትህ ባደረብህ የመቆርቆር ስሜት ነው። ለዚህ ጉዳይ ችግሩንና መፍትሔውን ደህና አድርገህ

ስለአጠናኸው፣ አሁን ዘርዝረህ ባስረዳኸን መሠረት ማስታወሻውን
አዘጋጅልኝና ለዋናው ዲሬክተራችን ለሙሴ ደልቢ አቅርቤ አንድ ውሳኔ እንዲሰጡበት አደርጋለሁ።

ስማ ! አቶ መኰንን ! ከዚህ ሌላ ስለ አንተ መናገር ወይም መናዘዝ የምፈልገው ነገር አለ። ገና ከመጀመሪያው፣ ከዚህ ላጋር ጉምሩክ ሥራ ለመጠየቅ ማመልከቻህን ይዘህ እኔ ቢሮ ስትቀርብ፣ የተናገርከውን መቸውንም አልረሳውም። እኔ ሁኔታህን ስመለከት፣ ችግር ያጠቃህ ሳትሆን አትቀርም ብዬ፣ ችሎታህም ለሒሳብ ሠራተኛነት በቂ መሆኑን ገምቼ፣ ነገ መጥተህ ሥራህን እንድትጀምር የምሥራቹን ስነግርህ፣ « ... የለም ! ፈተና ቀርቤ በደንቡ መሠረት ፈተናውን ሳላልፍ ሥራ አልቀበልም ... » ስትለኝ፣ ይህን ዓይነቱን ሰው ከዚህ ቀደም አይቼው ! ሰምቼው ! ስለማላውቅ ከመጠን በላይ ተገረምኩ። የተገረምኩትም፣ እኔ የመንግሥት ባለሥልጣን ደንብ አፍራሽ ስሆን፣ አንተ አንድ ተራ ሰው ከራስህ ጥቅም ይበልጥ ደንብ አክባሪ ሆነህ በመገኘትህ ነው። ሒሳብህን ካዳመጥኩ በኋላ፣ ሌላ ክርክር ውስጥ ሳልገባ ፈተና እንዲሰጥህ ወደ ሙሴ ፋዋድ መራሁህ። በዚህ ጊዜ ስለአንተ አድሮብኝ የነበረው ስሜት፣ "ይኸ ሰው" በተፈጥሮው ጠማማና ነገረኛ ሊሆን ይችላል። ወይም ደግሞ ሐቀኛና ቁም ነገረኛ ሊሆን ይችላል የሚል ነበር። ከፈተናው በኋላ ደግሞ ሙሴ ፋዋድ በገለጸልኝ አስተያየት ሰውየው ለሒሳብ ሥራ ችሎታው በቂ ነው። ነገር ግን በጠባይ አስቸጋሪና ሞገደኛ ሳይሆን አይቀርም አለኝ። በበኩሌ ይህን ሁሉ ካመዛዘንኩ በኋላ፣ ይኸ ሰው ችሎታው በቂ ሆኖ በጠባይ በኩል የተወሰደበት አስተያየት፣ ትክክለኛው ሁኔታ ምን እንደሆነ ማወቅ የሚቻለው በሥራ ላይ ስለሆነ፣ ለጊዜው ቢሮ ይሰጠውና የሒሳብ ሥራውን ይጀምር ብዬ ወሰንኩ።

እንግዲህ ! ይኸውላችሁ። በእግዚአብሔር እርዳታ ሁላችንም ከተሳሳተ ፍርድ ድነናል። እኔና አማካሪዬ የዚህን ሰው ትክክለኛ ሁኔታ በሚገባ ሳናጠና የሥራ ዕድሉን ዘግተንበት ቢሆንኖሮ፣ ይህንን የመሰለ ለመሥሪያ ቤታችን ዕድገት፣ ለአገራችን ጥቅም የሚረዳ፣ መልካም ሐሳብ ከየት እናገኝ ነበር ? ... አቶ መኰንን ! ጉበዝ ነህ። ጨዋ ነህ። አገርህን ትወዳለህ። ሥራህን ታከብራለህ። በዚሁ ቀጥል፤ ትልቅ ቦታ ትደርሳለህ። ... በሚል ቃል ስብሰባው መፈጸሙን አስታወቁ።

## መኰንን ሀብተወልድ በጉምሩክ ዋና መሥሪያ ቤት የገቢዎች ሒሳብ ሹም

በላጋር ጉምሩክ የሒሳብ ክፍል ረዳት ሆነው መሥራት በጀመሩ በጥቂት ወራት ውስጥ፣ መኰንን ሀብተወልድ ስለ ኮንትሮባንድ ንግድ መከላከያና ስለ ዲፕሎማቶች የቀረጥ ነፃ መብት አሠራር ያደረጉትን ጥናት፣ የጉምሩኮች ዋና ዲሬክተር ግብፃዊው ሙሴ ደልቢ በአድናቆት ተቀበለው። ወዲያውም፣ መኰንን ሀብተወልድ እቢሮዬ መጥቶ እንዳነጋግረው ሲል አዘዘ።

ጥቅምት 19 ቀን 1911 ዓ.ም ከጠዋቱ በአራት ሰዓት መኰንን ሀብተወልድ ከጉምሩኮች ዋና ዲሬክተር ቢሮ ገብተው ሰላምታ አቀረቡ። ሙሴ ደልቢ አቶ መኰንንን ሲያይ ዓይኑ እላያቸው ላይ ተተከለ። ከሦስት ዓመት በፊት በቁርጥማት

ሕመም ምክንያት ፍልውሃ እየተመላለሱ በሚጠመቁበት ጊዜ፣ መኰንን ሀብተወልድን ገንዘብ ተቀባይ ሆነው ሲሠሩ አውቋቸው ነበር።

ደልቢ -- ሳይህ የማውቅህ መሰለኝ !

መኰንን -- አዎን ! ፍልውሃ ገንዘብ ተቀባይ ሆኜ ስሠራ ያስታውሱኝ ይሆናል።

ደልቢ -- ልክ ነው። እዚያ ነው ያወቅኩህ። ፍልውሃ ስንት ጊዜ ከሠራህ በኋላ ነው ላጋር ጉምሩክ የተቀጠርከው ?

መኰንን -- ከሦስት ዓመት በኋላ ነው።

ደልቢ -- ታዲያ እስካሁን ድረስ ለምን ሳትጠይቀኝ ቀረህ ?

መኰንን -- መጀመሪያ ማስቸገር አልፈለግኩም። ቀጥሎ ደግሞ እርስዎ ዘንድ የሚያስመጣ ጉዳይ አላጋጠመኝም።

ደልቢ -- ይኸው አሁን መጣህ አይደለም ?

መኰንን -- የመጣሁት እርስዎ ስለአስጠሩኝ ነው።

ደልቢ -- ባልጠራህ ኖሮ እኔን ለማየት አትመጣም ነበር ማለት ነው ?

መኰንን -- ቅድም እንዳልኩት ወደ እርስዎ የሚያስመጣ አቤቱታ ወይም የተለየ ጉዳይ ስለሌለኝ፣ እንዲሁ ጥቂት ያውቁኝ ነበር ብዬ ለሰላምታ እየመጣሁ ጊዜዎን ማባከን አልፈለግኩም። ይሁን
እንጂ፣ ስለርስዎ በግሌ ከፍ ያለ አስተያየትና ማስታወሻ ያለኝ ሰው ነኝ።

ደልቢ -- ስለ እኔ ከፍ ያለ አስተያየት ያለህ፣ የመንግሥት ከፍተኛ ባለሥልጣን ስለሆንኩ ነው ? ወይስ በሌላ ምክንያት ነው ?

መኰንን -- እንደሚያውቁት ለሰው መልካም አስተያየት ለመስጠት መለኪያው ባለሥልጣን በመሆን ብቻ አይደለም። ተራም ሰው ቢሆን፣ ጨዋነት፣ ቁም ነገረኛነትና ጠንካራ ዕምነት ካሳየ፣ ትልቅ ሰው ነው ተብሎ መልካም አስተያየት ሊያገኝ ይችላል። እኔ በርስዎ ላይ በግሌ የተለየ አስተያየት ያደረብኝ፣ ፍልውሃ ገንዘብ ተቀባይ ሆኜ በምሠራበት ጊዜ አንድ የማልረሳው ማስታወሻ ስለጣሉብኝ ነው።

ደልቢ -- ይህ ማስታወሻ ምን ኖርዋል?

መኰንን -- ከሦስት ዓመታት በፊት እርስዎ ፍልውሃ ለመጠመቅ በሚመጡበት ሰሞን አንድ ቀን ስለ ግል ሕይወቴ ሲያነጋግሩኝ፣ ከሌሊቱ ዐሥር ሰዓት ጀምሮ እስከ እኩለ ቀን ድረስ ከሠራሁ በኋላ ፣ አሊያንስ ፍራንሴዝ እየሄድኩ የፈረንሣዊኛ ቋንቋና ሒሳብ ሳጠና እንደማመሽ ገለጽኩልዎ። በዚህ ጊዜ የጀመርኩት በጣም ጥሩ

መሆኑንና ጠንክሬ እንድማር ካበረታቱኝ በኋላ፣ ቆይ ! ... እሽ ! የሚል ቃል ጠቅሰው ተለያየን። ይህ ቆይ ! ... እሽ ! ... ምን ማለት እንደሆነ ለማወቅ ባሰላስል፣ ለጊዜው መልስ ሳላገኝለት ቀረሁ። በሦስተኛው ቀን እንደተለመደው እርስዎ ወደ ፍልውሃ ሲመጡ፣ ብዙዎች ሉክ ወረቀቶችና እርሳሶች፣ ከነዚህም ጋር አንድ ጥሩ የሆነ ማሽ* በአሽከርዎ አስይዘው እነዚህን ያመጣኋቸው ለአንተ ነውና ተቀበል አሉኝ። ወረቀቶቹና እርሳሶቹ ለመማሪያዬ፣ ማሾው ደግሞ ማታ ማታ ለማጥኒያዬ አስበው ያዘጋጁልኝ ስለሆነ ልገልጸው ከምችለው በላይ ደስ አለኝ። ከዚያን ዕለት ጀምሮ አሊያንስ ፍራንሴዝ በቆየሁበት በሁለት ዓመት ጊዜ ውስጥ፣ እርስዎ አስበው ከሰጡኝ ወረቀቶችና እርሳሶች ሌላ ተጨማሪ መግዛት አላስፈለገኝም። ማሾውም ጥሩ መታሰቢያ ስለሆነ በጥንቃቄ ይገኛዋለሁ።

ደልበ. -- በውነት ይህንን ሁሉ በቁም ነገር ይዘህ ስለአስታወስከኝ እኔም ደስታዬን እገልጥልሃለሁ። ወደፊትም በሥራ ብቻ ሳይሆን በግልም ወዳጅነታችን እንደሚቀጥል ተስፋ አለኝ። በጣም ብርቱና አስተዋይ በመሆንህ በላጋር ጉምሩክ በተቀጠርክ በጥቂት ሳምንታት ውስጥ፣ ስለ ኮንትረባንድ ንግድ መከላከያና ስለ ቀንስሎች የቀረጥ ነፃ መብት አሠራር ያደረግከውን ጥናት አይቼ በጣም አድንቂያለሁ። አድናቆቴም ምን ያህል ለመንግሥትህ የምታስብና በሥራህም ጠንካራ ሰው በመሆንህ ነው።

ዛሬ የጠራሁህ በዚህ በዋናው መሥሪያ ቤት የገቢዎች ሒሳብ ሹም ሆነህ እንድትሠራ መወሰኑን ልነግርህ ነው። ከዚህ ቀደም እዚያ ላጋር ጉምሩክ ስትቀጠር ፈተና ተሰጥቶኝ ካላለፍኩ ሥራ አልቀበልም ብለህ ሹማምንቶቹን እንደረበሽካቸው ሁሉ እኔንም ሳልፈተን ሥራውን አልቀበልም ብለህ እንደማታስቸግረኝ ተስፋ አለኝ።

መኰንን -- እግዚአብሔር ይስጥልኝ ብዬ የጣሉብኝን ኃላፊነት በደስታ እቀበላለሁ። ላጋር ጉምሩክ እንድቀጠር ማመልከቻ ሳቀርብ፣ ፈተና ተሰጥቶኝ ችሎታዬ እንዲታወቅ የተከራከርኩት፣ በዚያን ጊዜ ደንቡ እንዳይዛነፍ ብዬ ነው። ዛሬ ግን እርስዎ የሰጡኝ ሹመት ነው። ለሹመት ደግሞ ፈተና አስፈላጊ ስላልሆነ፣ የሰጡኝን በደስታ ከመቀበል በስተቀር ሌላ ጥያቄ አላቀርብም።

ደልበ. -- ዕድሜህ ስንት ነው?

መኰንን -- የሚገርምዎት ይህን ሹመት የሚሰጡኝ ዛሬ ጥቅምት 19 ቀን በልደቴ ዕለት ነው። ዛሬ ልክ ሐያ አምስት ዓመቴ ነው።

ደልበ. -- በውነት ታሪክ ነው። በተወለድክበት ዕለት ለመጀመሪያ ጊዜ ሹመት ማግኘትህ በጣም የሚያስደስት ነው። .... እንግዲህ ከነገ ጀምሮ አዲስ ሥራህን ጀምር ብሎ አሰናበታቸው።

---

* መብራት

# የእኔ ዕድል ማለፊያ ሆነ። እንግዲህ! ለወንድሞቼ ላስብ !

*መ.ሀ.ወ*

መኰንን ሀብተወልድ ጥቅምት 19 ቀን 1911 ዓ.ም የሐያ አምስተኛውን ዓመት ልደታቸውን በሚያከብሩበት ዕለት የጉምሩክ ዋና መሥሪያ ቤት የሒሳብ ሹም ተብለው ሲሾሙ፣ አባታቸው አለቃ ሀብተወልድ ከዚህ ዓለም በሞት ከተለዩ ስምንት ወራት ሆኗቸው ነበር። መኰንን አዲሱ ሥራቸውን እንደተረከቡ፣ በመጀመሪያ ያለ አባት ብቻቸውን ለሆኑት ለትንንሾቹ ወንድሞቻቸው የወደፊት ዕድል ተጨነቁ። እነዚህም፣ የታላቅ እህታቸው የወይዘሮ ደብሪቱ ሀብተወልድ ልጅ መክብብ ዳምጤና ወንድማቸው አካለወርቅ ሀብተወልድ የዘጠኝ ዓመት ልጆች ሲሆኑ፣ ትንሹ ወንድማቸው አክሊሉ ሀብተወልድ ደግሞ የስድስት ዓመት ልጅ ነበር። « ... እነዚህን ሦስት ልጆች ከባላገር አምጥቼ፣ አዲስ አበባ ዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት አስገብቼ፣ ፈረንሣዊኛ እንዲማሩ ባደርግ፣ ምናልባት ዕድላቸው አምሮ ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ፈረንጅ አገር ለመሄድ ይችሉ ይሆናል። እኔም፣ በዚህ መንገድ የዕድላቸውን በር ለመክፈት ከቻልኩ፣ በሕይወት ዘመኔ ለቤተሰቦቼ አንድ ቁም ነገር እንደሠራሁ ልቆጥረው እችላለሁ ... » ብለው፣ መኰንን ሀብተወልድ ምኞታቸውን ዘረጉ። እሳቸው እራሳቸው ዕድላቸው ተቃንቶ፣ በጥቂት ዓመታት ውስጥ በገጠር ከአሥራት* ጸሐፊነት ተነሥተው፣ በፍልውሃ ገንዘብ ተቀባይነት አልፈው፣ የጉምሩክ ዋና መሥሪያ ቤት ሒሳብ ሹም ለመሆን ሲበቁ፣ ለኑሮአቸው መሻሻል ከመጣር በፊት ትንንሾቹን ወንድሞቻቸውን ከባላገር አምጥተው ለማስተማር ማሰባቸው፤ ትልቅ ቁም ነገር መሆኑ ይታያል።

እንግዲህ ! ሐሳቡ በጣም ጥሩ ነው። አፈጻጸሙ እንዴት ይሆናል? ኃይለኛዋ ቡልጊት እናታቸው ወይዘሮ ያደግድጉ ፍልፍሉ የመኰንንን ሐሳብ ተቀብለው እነዚህ ሦስት ልጆች ለፈረንጅ ትምህርት ወደ አዲስ አበባ እንዲመጡ ይለቋቸዋል ወይ? ... ትልቁ ጥያቄ እዚህ ላይ ነበር። ወይዘሮ ያደግድጉ፣ ባለቤታቸው አለቃ ሀብተወልድ ሀብቴነህ ከሞቱባቸው በኋላ፣ ስለነዚህ ሦስት ልጆች ዕድገት ያላቸው ሐሳብ፣ ከመኰንን ምኞት ጋር ጨርሶ የሚቀራረብ አልነበረም። መክብብ፣ አካለወርቅና አክሊሉ ወደ እንጦጦ ራጉኤል ተወስደው በዚያው እየኖሩ የቤተክህነት ትምህርት እንዲማሩና የአባታቸውን እርዓያ በመከተል መጀመሪያ በድቁና፣ ቀጥሎም በደብተራነት መልአከ ኃይል ራጉኤልን እንዲያገለግሉ፣ እመት ያደግድጉ የሚመስላቸውን እርምጃ ወስደዋል።

መኰንን ሀብተወልድ ይህንን አልሰሙም። አዲሱ ሥራቸውን ከተረከቡ ከሁለት ወራት በኋላ፣ እናታቸውን ወይዘሮ ያደግድጉን ለገና በዓል እንኳን ለብርሃነ ልደቱ አደረሰሽ ለማለት ታህሣሥ 28 ቀን 1911 ዓ.ም ደንቢ ሲደርሱ፣ ከእህቶቻቸው ከወይዘሮ የሺእመቤትና ይመኙሻል በስተቀር፣ እነዚያን ለወደፊቱ ዕድላቸው የሚጨነቁላቸውን ትንንሾቹን ወንድሞቻቸውን ሳያገኟቸው ቀሩ። የት ሄዱ ? ... ብለው ቢጠይቁ፣ መክብብ፣ አካለወርቅና አክሊሉ ካለፈው ወር ጀምሮ ወደ እንጦጦ ራጉኤል ተወስደው በመማር ላይ ናቸው፣ የሚል መልስ ተሰጣቸው። መኰንን በጣም ደነገጡ። በጣምም አዘኑ። እሳቸው ራሳቸው፣ ዝቋላ ወንበር

---

* ግብር

ማርያም ተልከው በሚማሩበት ጊዜ፣ በአስተማሪዎቹ ጭካኔ ምን ያህል እንደተሰቃዩና በዕለት ሕይወታቸውም ላይ ምን ያህል ችግር እንደነበረባቸው ትዝ አላቸው። ፊታቸውን ወደ እናታቸው መልሰው፣ ምነው እምዬ? ያለሁሽ አንጋፋው ልጅሽ እኔ ነኝ። እነዚህን ልጆች የአባታችን ምትክ ሆኜ እንዳስተምራቸውና ለወግ እንዳበቃቸው፣ ለምን አደራውን አልጣልሽብኝም? ብለው ጠየቁ። ወይዘሮ ያደግድጉ ስለ መኰንን ልጃቸው የአዲስ አበባ ኑሮ አንዳንድ ደስ የማይሉ ወሬዎች ሰምተው ስለነበረ፣ ለቀረበላቸው ጥያቄ የሰጡት መልስ አስደንጋጭ ሆነ። « ... **መጀመሪያ ልጆቼን እንኳንስ ለአንተ አደራ ልሰጥ ይቅርና፣ አንተን ራስህን አደራ ብዬ ለመስጠት የሚቀበለኝ ሰው ባገኝ ፈጣሪዬን ምን ያህል ባመሰገንኩት ነበር ? ...** » አሏቸው።

<u>መኰንን፣</u> እናቴ እስከዚህ ድረስ በምሬት ለመናገር ያበቃሽ ምክንያቱ ምንድን ነው ?

<u>ያደግድጉ፣</u> ያላደረግከው ምን አለ ? ያንተ ጉድ መቼ ተዘርዝሮ ያልቃል ?

<u>መኰንን፣</u> የሰማሽውን ገልጠሽ ካልነገርሽኝ እዚህ ቤት አላድርም፤ ወደመጣሁበት እመለሳለሁ።

<u>ያደግድጉ፣</u> አንደኛ/ በመታመምህ ምክንያት አዲስ አበባ እየታከምክ እንድትኖር ወንድምህ የአለቃ ደስታ ልጅ በፍልውሃ ጠበል ሥራ ቢሰጥህ፣ የፈረንጅ ትምህርት ካልተማርኩ ብለህ ስታስቸግረው ኖርክ። ቀጥሎ ደግሞ ትምህርቱ ሲሆንልህ፣ በድንገት ሌላ ሥራ አገኘሁ ብለህ ጥለኸው ሄድክ። በውነት ብታስበው ይህን ማድረግህ ጥሩ ነው? የሀብተወልድ ልጅ ለጥቅሙ ሲል፣ በችግር ጊዜ የደረሰለትን ወንድሙን መክዳት ይገባዋል? ይህን ሰምቼ በጣም አዝኜብሃለሁ።

ሁለተኛ/ ሌላው ያሳዘነኝ ነገር፤ አሩሲ ሆነህ ስለወለድከው ልጅ ነው። በሕመምህ ምክንያት አንተው ፈልገህ ካገባሀት ሚስትህ ከተፋታህ በኋላ፣ በሕይወት የተረፈልህ ልጅህ (ከበደ) እኛ ዘንድ መጥቶ እንዲያድግ አባትህ ደጋግመው አደራ ብለውህ ነበር። ይኸው ከሦስት ዓመት በላይ ሆነ። ምንም ሳታደርግ ልጅህ እዚያው በእንጀራ አባት እየተሰቃየ ይኖራል አሉ። እንግዲህ፣ ይህን የመሳሰለ መላ ቅጥ የሌለው ነገር እየሠራህ፣ አንዴ ወዲያ አንዴ ወዲህ እያልክ፣ እንደ ዘላን የምታድር ሰው፣እንዴት አድርገህ ነው? እነዚህን ባለመታደል አባታቸውን ያጡ ወንድሞችህን አሳድጌ ለወግ አበቃቸዋለሁ የምትለኝ ? ይኸ ጨርሶ የማይታሰብ ነው። ከዚህ ሁሉ ይልቅ አንተ እንደሌላው ሰው፣ አንድ ቦታ ሠርተህ፣ አንድ ቦታ ረግተህ፣ የምትኖር ሆነህ እንዳይህ ፈጣሪዬን በጸሎቴ ባስቸግረው የተሻለ ይመስለኛል።

መኰንን ሀብተወልድ ይህ የእናታቸው አነጋገር ያልጠበቁት ሆኖ ስለአስደነገጣቸው፣ የወንድሞቻቸውን ወደ አዲስ አበባ መውሰድ ጉዳይ ለጊዜው መነጋገሩን ትተው፣ እናታቸው አንዳንድ ተንኰለኞች የነገሯቸው ሁሉ ከእውነት የራቀ የፈጠራ ወሬ መሆኑን ለማሳመን ቅድሚያ ሰጡ።



የመኰንን ሀብተወልድ ቤተሰቦች፤

ከቀኝ ወደ ግራ ወንበር የያዙት አቶ መኰንን ሀብተወልድ ሲሆኑ፤ ከእሳቸው ቀጥሎ ያሉት እናታቸው ወ/ሮ ያደግድጉ ፍልፍሉ ናቸው። ከዚያም በስተጀርባ ከቆሙት ቤተሰቦች መካከል ታናናሽ ወንድሞቻቸው መክብብ፣ አካለወርቅና አክሊሉ ይገኛሉ።

« ... ወንድሜ ወዳጄ አቶ በቀለ ደስታ በዚያ በችግሬ ጊዜ በፍልውሃ እንድሠራ በማስቀጠር ብቻ ሳይሆን፣ ለመኖሪያዬም አስቦ ቤት በነፃ በመስጠት ያደረገልኝን ውለታ አልረሳሁም። ነገም ወደፊትም አልረሳውም። እንደሰማሽው የኔ ሥራ የፍልውሃ መግቢያ ገንዘብ ተቀባይነት ስለሆነ፣ ሳይነጋ ከሌሊቱ ዐሥር ሰዓት እየተነሣሁ ያ ሁሉ የሟት ውርጭ እያሰቃየኝ፣ እስከ እኩለ ቀን ድረስ ሳልነቃነቅ ቆሜ እሠራ ነበር። ከእኩለ ቀን በኋላ ግን ነፃ ነኝ። በዚህ በግማሹ ቀን ዕረፍቴ፣ ተማሪ ቤት ገብቼ የሒሳብና የፈረንሣዊኛ ቋንቋ ለማጥናት የቻልኩት፣ ወንድሜ በቀለን በማስቸገር ሳይሆን፣ እሱ ራሱ ከልቡ አስቦ ስለፈቀደልኝ ነው። በጠቅላላው ሦስት ዓመት ያህል በፍልውሃ ከሠራሁ በኋላ፣ ወደ ሌላ የመንግሥት መሥሪያ ቤት የተዛወርኩት፣ ከወንድሜ ከበቀለ ተደብቄ አይደለም። « ... ሌሊት ሳትተኛ በውርጭ እየተጠቃህ ትኖር ነበር። አሁን የቢሮ ውስጥ ሥራ ማግኘትህ፣ የአባትህ አምላክ ስለረዳህ ነው ... » ብሎ መርቆ አሰናብቶኛል። ፍልውሃ የወንድሜ የበቀለ የግል ቤቱ አይደለም። የመንግሥት ቤት ነው። እኔም የተዛወርኩት ከመንግሥት ቤት ወደሌላው የመንግሥት ቤት ስለሆነ፣ እንደ ግል ቤት ሠራተኛ፣ ጌታውን ከድቶ ወደ ሌላ ጌታ እንደሄደ ዓይነት፣ የምቆጠር አይደለሁም። ... ስለዚህ እናቴ፣ እውነተኛውን ነገር ባለመረዳት በእኔ በልጅሽ ላይ ማዘን የለብሽም። ለዚህ ለዘንድሮው ልደት በዓል ለመጀመሪያ ጊዜ አባታችን በሌሉበት ብቻሽን ትሆኛለሽ ብዬ ብመጣ፣ ነገር ቋጥረሽ ስለጠበቅሽኝ ማዘን ያለብኝ እኔ ነኝ። ... »

ወይዘሮ ያደግድጉ ልጃቸው በሰጧቸው ማብራሪያ ይህን ያህል አልረኩም። « .... እኔ ነገር ቋጥሬ አልጠበቅኩህም። እቤቴ ድረስ ተጉዞ የመጣልኝን ወሬ ሳልደብቅ ነግሬሃለሁ። አንተም ያስረዳኸኝን አዳምጫለሁ። እንዳልከው ከሆነ ማለፊያ ነው። ይልቅ፣ ለገና በዓል እንቺን ለመጠየቅ መጣሁ፣ የምትለውን ልቤ አልተቀበለውም። አባትህ አለቃ ሀብተወልድ ከሞቱ በኋላ፣ የትንሣኤን በዓል፣ የዘመን መለወጫን በዓል፣ የመስቀልን በዓል፣ ብቻዬን ተከራምቼ ሳሳልፍ፣ መቼ መጥተህ አየኸኝ? .... ዛሬ የመጣኸው፣ እነዚያን ልጆቼን ይዘህ ለመሄድ መሆኑ ገብቶኛል። ይኸ ሐሳብህ ደግሞ አይሳካልህም። ብትወድም ባትወድም፣ ስመጥሩው አለቃ ሀብተወልድ ተተኪ የሚኖራቸው ከእነዚህ ልጆች መካከል ነው .... » አሏቸው። አቶ መኰንን የመጣሁት ልጆች ለመውሰድ አይደለም ብለው ቢከራከሩም፣ እናታቸው አላመኗቸውም። ገና ስትመጣ፣ እቤት እንደገባህ ልጆቹን ስታጣቸው የታየብህ ድንጋጤ፣ ያሰብከውን የሚናገር ነው ብለው ዘጉባቸው።

## መኰንን ሀብተወልድ ከመምሬ ገብረዮሐንስ ጋር

መምሬ ገብረዮሐንስ የወይዘሮ ያደግድጉ የንስሐ አባት ናቸው። አለቃ ሀብተወልድ ከሞቱ በኋላ፣ ለቤተሰቡ ጉዳይ ዋና አማካሪና ተጠሪ ሆነዋል። መኰንን ሀብተወልድ እናታቸውን አሸንፈው ወንድሞቻቸውን ለመውሰድ አለመቻላቸውን ሲረዱት፣ በንስሐ አባት በኩል ብሞክር፣ ያሰብኩት ይፈጸምልኝ ይሆናል የሚል ተስፋ አደረባቸው። በዚህ መሠረት በልደት በዓል ማግሥት፣ ታህሣሥ 30 ቀን 1911 ዓ.ም በአድዓ ወረዳ ውስጥ ጨለባ በተባለው ቀበሌ ከሚገኘው ከመምሬ ገብረዮሐንስ ቤት ደርሰው፣ ሦስቱን ወንድሞቻቸውን አዲስ አበባ ወስደው ለማስተማር ያሰቡትን እናታቸው ስለከለከሉ፣ የቄሱን አማላጅነት ጠየቁ።

መምሬ ገብረዮሐንስ በመጀመሪያ ደረጃ የቀረበውን ሐሳብ ለመደገፍ የሚፈልጉ አልመሰሉም ነበር። ከመወያየት ብዛት፣ መኰንን ሀብተወልድ በአዲስ አበባ የመንግሥት መሥሪያ ቤት ሹም በመሆናቸው፣ መምሬ ገብረዮሐንስ በገንዘብ ሚኒስቴር በኩል ላጋጠማቸው ችግር መፍትሔ እንደሚያስገኙላቸው ቃል ገቡላቸው። በዚህ ጊዜ፣ ቄሱ ወዲያውኑ ጥምጥማቸውን አሳምረው በስጋር በቅሎ እየገሰገሡ፣ የወይዘሮ ያደግድጉን ሐሳብ ለማስለወጥ ደንቢ ደረሱ። ወይዘሮ ያደግድጉ ያልጠበቋቸው እንግዳ በድንገት ብቅ ሲሉባቸው፣ ለልደት በዓል እንኳን አደረሰሽ ሊሉኝ ነው በማለት፣ ተጥረብርበው በጋለ ደስታ ተቀበሏቸው። ውስጡን ለቄስ እንደሚባለው፣ የንስሐ አባታቸው የመጡት፣ ለበዓሉ መልካም ምኞት ለመግለጥ ሳይሆን፣ መኰንን ትንንሾቹን ወንድሞቹን ለማስተማር ወደ አዲስ አበባ እንዲወስዳቸው ለማስማማት ሆኖ ተገኘ። ለዚህ መሆኑን ሲያውቁ፣ ወይዘሮ ያደግድጉ ብው አሉ። መጀመሪያ በልጃቸው በመኰንን በጣም አዘኑ። ሁለተኛ የንስሐ አባታቸው ለዚህ አማላጅ ሆነው መምጣቸው እጅግ አስገረማቸው። ሆኖም ወይዘሮ ያደግድጉ የሚያስቡትንና የሚያምኑበትን ከመግለጥ አልተቆጠቡም።

« .... መኰንን፣ በልጅነቱ በተስቦ በሽታ ስለተሠቃየና ሰውነቱ ስለደቀቀ፣ የስመ ጥር አባቱን ቦታ መያዝ አይችልም ተብሎ፣ ጤናው በሐኪም እየተጠበቀ አዲስ አበባ እንዲኖር ቢደረግ፣ አልፎ ተርፎ ለአለቃ ሀብተወልድ ምትክ የሚሆኑትን እነዚህን ልጆች ለማሰናከልና ፈረንጅ ተማሪ ቤት ጨምሮ ሃይማኖታቸውን ለማስለወጥ የሚደክም መሆኑን አውቂያለሁ። ይስሙኝ አባቴ! እኔ ሕይወቴ ቆማ ይሄ አይደረግም። እኔ ሕይወቴ ቆማ ይህን አላይም። እኔ የምመኘውና የምጸልየው፣ የሀብተወልድን ተተኪዎች አይቼ ለመሞት ነው። .... » መምሬ ገብረዮሐንስ የወይዘሮ ያደግድጉን ምሬት ካዳመጡ በኋላ፣ ሌላ የማሸነፊያ መንገድ ፈለጉ። መኰንን ያሰበውን በትክክል አልተረዳሽለትም። መጀመሪያ፣ ልጆቹ የሚማሩት የፈረንጅ ትምህርት ለሥልጣኔ የሚበጀውን ነው እንጂ፣ ሃይማኖትን ጨርሶ አይነካም። ሁለተኛ የሚማሩት የፈረንጅ ትምህርት፣ ከእኛ ትምህርት ጋር ተጣምሮ፣ ዜማውንም ቅኔውንም ጭምር ነው። ሦስተኛ፣ በዕረፍታቸውና በበዓላት ጊዜ ራጉኤል እየመጡ እንዲያገለግሉ ታስቦበታል አሏቸው። ወይዘሮ ያደግድጉ በዚህም አላመኑም። « ... እዬ አባቴ ! የሚነግሩኝ ሁሉ፣ እውነት ፍንጥቅ ብላ የማትታይባት የአፍ ታሪክ ነች። ፈረንጅና ሐበሻ ቀምሞ የሠራው ወጥ ጤነኛ ሰው የሚቀምሰው ይመስልዎታል ? ... እኔ አላምንም። እኔ አይታየኝም። እስቲ ልብ ብለው ይመልከቱት ? መኰንን፣ ለእነዚህ ልጆች ይህን ሁሉ አደርጋለሁ እያለ የሚለፈልፈው፣ እሱ ራሱ በዝቋላ ተምሮ በራጉኤል ቀድሶ ያከማቸውን ዕውቀት መቼ ሠራበት ? እስቲ እርስዎ አባታችን ይጠይቁት ? አዲስ አበባ እየኖረ ራጉኤልን እንኳንስ ለማገልገል፣ ለመሳለም ደርሶ ያውቃል ? ... እኔ ምንም መሃይምን ብሆን፣ ይህንን ያህል ነገር የማላስተውል አይደለሁም። አሁን ማን ይሙት? እነዚህ ልጆች አዲስ አበባ እያደጉ የራጉኤል አገልጋይዎች ይሆናሉ ? ... መልሱን እርስዎ ይድረሱበት ! .... » መምሬ ገብረዮሐንስ አልሸነፍም ብለው ክርክራቸውን ቀጠሉ። እሱም የማያዋጣ ሲሆንባቸው ወደ ልመና ገቡ። በዚህ ጊዜ ወይዘሮ ያደግድጉ ትንሽ ረገብ ብለው አንድ ትንሽ ስጦታ አደረጉ። « እንግዲያውስ አባቴ ይስሙኝ ! ከእነዚህ ከሦስቱ ልጆቼ መካከል፣ በጠባዩ ባይተዋርና ግዴለሽ የሆነ፣ በልቡ ምን እንደሚያስብ የማይታወቅ፣ የሚሰጠውን ትምህርት በቅጡ የማይቀበል፣ እንኳንስ ለትልቁ ለዜማና ለቅኔ ትምህርት፤ ዳዊት ለመድገም እንኳን ይደርሳል ብዬ የማላስበው አክሊል ስለሆነ፣ መኰንን እሱን ወስዶ የሚፈልገውን ያድርግ። መኩሪያና አካለወርቅ ግን፣ ቀለም ተቀባይነታቸው የሚያስደስት፣ ትጋትና ንቃት የሚታይባቸው ስለሆኑ፣ የአባታቸው ምትክ ሆነው ራጉኤልን ያገለግላሉ

ብዬ ተስፋ አድርጌባቸዋለሁ። እንግዲህ ! መኮንን አክሊሉን ይውሰድ። ከዚህ ሌላ ምንም ነገር መጠየቅም፣ መነጋገርም አያስፈልግም ›› ብለው የቆረጠ ሁኔታ አሳዩ። እዚህ ላይ መምሬ ገብረዮሐንስም ትንሽ ደነገጡ። ይህች ሴት ቆርጣለች። መስቀሌን እንሥቼ ገዝቼሻለሁ ብላት፣ አልቀበልህም ብላ ልታሳፍረኝ ትችላለች። ስለዚህ የአክሊልን ስጦታ ተቀብያለሁ ብለው ማመስገንና በደህና መንፈስ መለያየትን መረጡ።

## አክሊል ብቻውን !

በንስሐ አባት በመምሬ ገብረዮሐንስ ብርታት የእመይቴ የወይዘሮ ያደግድጉ ፈቃድ ከተገኘ በኋላ፣ መኮንን ሀብተወልድ አክሊሉን ለማምጣት ጥር 11 ቀን 1911 ዓ.ም በጥምቀት በዓል እንጦጦ ራጉኤል ሄዱ። እዚያ እንደደረሱ፣ የሦስቱ ወንድሞቻቸው አኗኗር በጣም የሚያሳዝን ሆኖ ታያቸው። ቀን ሲማሩ የሚውሉበት ቦታ ማታ የሚተኙበት መደብና ቆርበት፣ በቀን ሁለት ጊዜ የሚዘጋጅላቸው የዳቤ ምግብ*፣ የችግረኞቹን ዘኬ ለቃሚዎች የሚባሉትን ተማሪዎች ሕይወት መስሎ ታያቸው። እርግጥ ነው ! በአገራችን ቤተሰብ አስተያየት፣ ተቀማጥሎ ካደገው ይልቅ፣ ችግርን የቀመሰና ያየ ልጅ ጨዋና ግብረገብ ይሆናል ተብሎ ይታመናል። በብዙ ረገድ ውጤትም ሰጥቶ ታይቷል። ሆኖም በአድዓ ደንቢና በጨለባ ሁለት ጋሻ ለም መሬት እያረሱ ብዙ ምርት ያላቸው ቤተሰቦች፣ ልጆቻቸውን እስከዚህ ድረስ በችግር መቆላት የሚገባ አይደለም። አባታችን ቢኖሩ ይህ አይደርስም ነበር። እናታችን ተሳስታለች ብለው፣ መኮንን ሀብተወልድ ኃዘን ተሰማቸው። በዚህ ላይ ደግሞ፣ አክሊሉ፣ ከወንድሞቼ ከአካለወርቅና ከመክብብ ተለይቼ ከአንተ ጋር አልሄድም አላቸው። መክብብና አካለወርቅም፣ አክሊል ከእኛ ተነጥሎ መሄድ የለበትም ብለው ጮኹባቸው። እምዬ ያደግድጉ ለአሁኑ የፈቀዱልኝ አክሊልን ብቻ እንድወስድ ነው። ሌሎቻችሁን ቢበዛ ከሁለት ወር በኋላ እንድወስዳችሁ እምዬ ተስፋ ሰጥተውኛል እያሉ፣ ለማባበል ቢሞክሩም፣ ከሄድን አንድነት፣ ከቀረን አንድነት፣ ነው ብለው ሦስቱም በአንድ ድምፅ ተባበሩ።

አቶ መኮንን የልጆቹን መለያየት ቀድሞውንም አልወደዱትም ነበር። ልጆቹም አንለያይም ብለው መጠንከራቸው በአንድ በኩል አስደስቷቸዋል። እንግዲህ ምን ማድረግ ይቻላል? … የደረሰ ይድረስ ብለው ሦስቱንም ልጆች ቢወስዱ፣ የእመይቴ ያደግድጉ እርግማን ይቀስፈኝ ይሆናል ብለው ፈሩ። ከዚህ በላይ ደግሞ ልጆቹን ዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ለማስገባት አሁን የትምህርቱ ዓመት ስለተጋመሰ፣ መጭውን መስከረም መጠበቅ ያስፈልጋል። ስለዚህ እስከዚያ ድረስ እናቴን እየተለማመጥኩ በተስፋ መጠበቅ ይሻል ይሆናል ብለው ወሰኑ። የልጆቹ አኗኗር ግን በጣም ስለአሳሰባቸው፣ ምግባቸውና መኝታቸው እንዲሻሻልላቸው በየወሩ ገንዘብ ለመክፈል፣ ከጠባቂዎቻቸውና ከአስተማሪዎቻቸው ጋር ስምምነት አድርገው ወደ አዲስ አበባ ተመለሱ።

* ወፍራም እንጀራ

# የቃና ዘገሊላ በዓል ተአምር

ጥር 14 ቀን 1911 ዓ.ም መኰንን ሀብተወልድ በጉምሩክ ቢሮአቸው ሲሠሩ ውለው ወደማታ እቤታቸው ሲመለሱ፣ አንድ መላክተኛ ከአድዓ ጨለባ በፈረስ እየጋለበ መጥቶ፣ ከእናታቸው የንስሐ አባት ከመምሬ ገብረዮሐንስ የተጻፈ ደብዳቤ ሰጣቸው።

**ይድረስ ከልጄ ከመኰንን ሀብተወልድ፣**

እንደምን አድረሀ ውለሃል። እኔ በሥላሴዎች ቸርነት ደህና ነኝ። ይኸን ደብዳቤ የጻፍኩልህ አንድ የምሥራች ልነግርህ ነው። ያች ጻድቅ እናትህ እመት ያደግድጉ ጥር ዐሥራ አንድ ለዐሥራ ሁለት ለቅዱስ ሚካኤል አጥቢያ፤ አንድ ድንቅ ታሪክ የሆነ ሕልም አይታ ትናንት እዚህ ድረስ መጥታ ነገረችኝ። አንተ ! መኰንን ሀብተወልድ፣ በአብደላ ካኔ* ቀሚስ አሸብርቀህ፣ በወርቀዘቦ የተጠለፈ ካባ ደርበህ፣ ባርኔጣ አድርገህ፣ ሦስቱን ወንድሞችህን አስከትለህ፣ ትልቁን ቤተ መንግሥት እየዞርክ ቀላድ* ስትጥል አይታሀለች። ሕልሟ ግልጽ ነው ፈች አያስፈልገውም። እነዚህ ወንድሞችህ ዕድላቸው በአንተ እጅ መሆኑን ቸሩ ፈጣሪያችን እንደነገራት ተረድታዋለች። ባለፈው ጊዜ ነገሩ ሳይገባኝ ያስቀየምኩህን ይቅርታ አድርግልኝ እያለች፣ ልጆቹን ወስደህ ያሰብከውን እንድታደርግላቸው ፈቅዳልሃለች። አንድ ነገር ብቻ፣ በተሰቀለው ጌታ፣ ደሙ በፈሰሰው፣ አጥንቱ በተከስከሰው ብላ፣ አጥብቃ የምትለምንህ፣ እነዚህ ልጆች ምንም እንኳ የምንወደው የቅዱስ ራጉኤል አገልጋዮች ይሆናሉ ብዬ ባላስብም፣ ሃይማኖታችንን ጠብቀው እንዲኖሩ አደራ ብላሃለች። እንግዲህ፣ አንተ የተጨነቅክበትንና የለፋህበትን እግዚአብሔር በቸርነቱ
ስለአቃናልህ፣ እኔም ደስታዬንና ምርቃቴን እልክልሃለሁ። ልጆቹን ጊዜ ሳታባክን በቶሎ ውሰዳቸው።

አባትህ መምህር ገብረዮሐንስ

ይህን ደብዳቤ በምሽት ካነበቡ በኋላ፣ መኰንን ሀብተወልድ ከደስታቸው ብዛት እንቅልፍ አጥተው አደሩ። በማግሥቱ ጠዋት በሦስት ሰዓት አለቃቸው ሙሴ
ደልቤ ቢሮ ገብተው፣ ወንድሞቻቸውን ለመውሰድ እናታቸው ስለተስማሙ፣ እንጦጦ ወጥተው ይዘዋቸው ለመምጣት የአንድ ቀን ፈቃድ ጠየቁ። መኰንን የገጠማቸውን ችግር፣ ደልቤ ቀደም ሲል የሚያውቀው ስለነበረ፣ የአንድ ቀን ፈቃድ ብቻ አይበቃህም አላቸው።

አንድ ቀን፣ ማረፊያቸውን ማዘጋጃ፣
አንድ ቀን፣ ከእንጦጦ ማምጫ፣
አንድ ቀን፣ ልብሶቻቸውን ማዘጋጃና ከተማውን ማስጐብኛ፣
አንድ ቀን፣ ለትምህርታቸው የሚያስፈልጉትን መጻሕፍት፤ ደብተሮችና፤ እርሳሶች ማሰናጃ፣

በድምሩ አምስት ቀናት ስለሚያስፈልጉህ ፈቃድ ሰጥቼሃለሁ ብሎ አሰናበታቸው። ይኸ ደግሞ ለመኰንን ሀብተወልድ ያልተጠበቀ ተጨማሪ ትልቅ ደስታ ሆነ።

---

* በዚያን ዘመን የነበረ የክብር ልብስ
* መሬት መለካት

# ሦስቱ ተማሪዎች

መኮብብ፣ አካለወርቅና አክሊሉ፣ ታላቅ ወንድማቸው መኰንን ሀብተወልድ፣ አባትም እናትም ሆነው እያስተማሩ ለማሳደግ ቅዳሜ ጥር 24 ቀን 1911 ዓ.ም ከእንጦጦ ራጉኤል ይዘዋቸው በበቅሎ ጉዞ አዲስ አበባ ሲደርሱ፣ እነዚህ ልጆች ለመጀመሪያ ጊዜ የሚያዩት የከተማው ውበት፤ ምን ያህል ገነት መስሎ እንደታያቸው በሕይወት ዘመናቸው ብዙ ጊዜ እያነሡ ይጨዋወቱ ነበር። ከዚህ አድናቆት በኋላ ደግሞ፣ ከመኖሪያቸው ከአቶ መኰንን ቤት ሲደርሱ፣ ቀድሞ በአድዓ ሆነ በእንጦጦ ራጉኤል ያላዩትንና ያልጠበቁትን የመኝታዎቻቸውን ዝግጅት ሲመለከቱ፣ እጅግ አድርገው ተገረሙ።

በአንድ ሰፊ ክፍል ውስጥ ሦስት የጠፍር አልጋዎች ከቃጫ ከተሠሩ ፍራሾች ጋር "ካሊም" በተባሉ ለስላሳ ምንጣፎችና ብርድ ልብሶች ተነጥፈው ጠብቀዋቸዋል። ከዚህ በቀር ደግሞ በየአልጋዎቻቸው ራስጌ ለትምህርታቸው ማጥኒያ አንዳንድ አነስተኛ ጠረጴዛና ወንበር ከማሾ መብራት ጋር ተዘጋጅቶላቸዋል። በየጠረጴዛው ላይም ደብተሮች፣ እርሳስና ወረቀቶች ተደርድረውላቸዋል። ለእነዚህ ልጆች ይህ ሁሉ ዝግጅት ከዚህ ቀደም ያላዩትና ያላለሙት አዲስ ነገር ሆነባቸው። "ደንቢ" ተወልደው ባደጉበት ዘመንና ከዚያም ወደ እንጦጦ ራጉኤል ተዛውረው በቆዩበት ጊዜ፣ የመኝታቸው ዝግጅት በድንጋይና በጭቃ ተገንብቶ በተለሰነ "መደብ" ላይ ሣር ተጉዝጉዞ፣ በላዩ ላይ ቁርበት ተነጥፎ፣ ከላይ እቤት ውስጥ ተፈትሎ የተሠራ ጋቢ እየለበሱ ይተኙ እንደነበረ ያስታውሳሉ። የአዲስ አበባው ዝግጅት ግን፣ አልጋውም ሆነ ፍራሹ፣ የካሊሙ ምንጣፍ ሆነ ብርድ ልብሱ፣ ከፍተኛ ምቾትና ንጽሕና ስላለው፣ የልጆቹ ደስታ ወሰን የሌለው ሆነ። በልብሶቻቸውም በኩል የሁለት ጊዜ መቀየሪያ የሚሆኗቸው ዘመናዊ ኮቶችና የቁምጣ ሱሪዎች፣ ከመርደፋና ከካኪ የጨርቅ ዓይነቶች እየተመረጠ፣ ልብስ ሰፊ እቤት ድረስ መጥቶ በየልካቸው ሰፍቶ ሰጣቸው። በዚህ አኳኋን ዝግጅቱ ከተጠናቀቀላቸው በኋላ፣ በመስከረም 1912 ዓ.ም በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት መደበኛ ትምህርታቸውን እስከሚጀምሩ ድረስ፣ ለስድስት ወራት ያህል አሊያንስ ፍራንሴዝ እየተመላለሱ የፈረንሣዊኛ ፊደልና ሒሳብ እያጠኑ እንዲቆዩ ተደረገ።

ሰኞ መስከረም 20 ቀን 1912 ዓ.ም ሦስቱ ሀብተወልዶች፣ በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ትምህርታቸውን ሲጀምሩ፣ ቀደም ሲል በአሊያንስ ፍራንሴዝ ለስድስት ወራት የፈረንሣይ ፊደልና ሒሳብ ሲያጠኑ በመቆየታቸው፣ ከሌሎቹ አዲስ ጀማሪዎች ከሆኑት ጓደኞቻቸው ይበልጥ በመምህራኖቹ ዘንድ የተሻለ ግምት ተሰጣቸው። በዚያን ዘመን የምኒልክ ተማሪ ቤት የትምህርት አሰጣጥ በፈረንሣዊኛና በእንግሊዝኛ ቋንቋዎች በሁለት ዓይነት ክፍሎች የተመደቡ ስለሆኑ፣ ከሦስቱ የሀብተወልድ ልጆች መካከል አካለወርቅ፣ ወደ እንግሊዝኛው ክፍል ካልተዛወርኩ ብሎ አስቸግሮ ነበር። አቶ መኰንን ግን፣ ሦስቱም ልጆች በውጭ አገር ትምህርት እንዲለያዩ አልፈለጉም። በእሳቸው አስተያየት፣ ሦስቱም አንድ ዓይነት ትምህርት መማራቸው፣

1ኛ/ የትምህርታቸውን አያያዝ ለመቆጣጠር ይመቻል።

2ኛ/ ሦስቱም በተማሪ ቤት የሚሰጣቸውን ትምህርት በየደብተራቸው

እየመዘገቡ እቤታቸው ሲመለሱ፣ በአንድነት ለማጥናትና አንዱ ያልገባውን ሌላው እያስረዳ ተባብረው ለመሥራት ያስችላቸዋል።

3ኛ/ ዕድላቸው አምሮ የአንደኛ ደረጃ ትምህርታቸውን በመልካም ውጤት ካጠናቀቁ፣ ወደፊት ለከፍተኛ ትምህርት በአንድነት ወደ ፈረንሣይ አገር ለመሄድ ይችላሉ፣ ብለው ስለወሰኑ፣ ሦስቱም ልጆች ሳይለያዩ የፈረንሣይ ተማሪዎች ሆነው ቀጠሉ።

## የመኰንን ሀብተወልድ ምክር

መኰንን ሀብተወልድ ሦስቱ ወንድሞቻቸው በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት የፈረንሣዊኛ ትምህርታቸውን ከቀጠሉ በኋላ፣ በየጊዜው የሚመክሯቸውና የሚቆጣጠሯቸው ተግተው በመማር ጥሩ ውጤት ይዘው እንዲገኙ ብቻ አልነበረም። በዚያን ዘመን የነበረችው ኢትዮጵያ፣ አስተዳደሯ በምን ሁኔታ ላይ እንደሚገኝና፣ የወደፊቷ ኢትዮጵያ ደግሞ የተማሩ ወጣቶች ሲደርሱላት በሥልጣኔ ምን ያህል ለመራመድ እንደምትችል፣ በወንድሞቻችው አዕምሮ ላይ እንዲቀረፅ ብዙ ለፍተዋል።

መክብብ፣ አካለወርቅና አክሊሉ፣ የአንደኛ ደረጃ ትምህርታቸውን ፈጽመው ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ፈረንጅ አገር እስከተላኩበት ድረስ፣ ወንድማቸው ቤት በኖሩበት በስምንቱ ዓመታት ዘመን ውስጥ ቢያንስ በወር አንድ ጊዜ፣ ለአንድ ሰዓት ተኩል የመኰንን ሀብተወልድ "ምክር መስጫ" የተባለ ፕሮግራም ይዘጋጅላቸው ነበር። በዚያን ዘመን የመኰንን ሀብተወልድ አስተሳሰብ ምን እንደሆነና፣ ለወንድሞቻቸውም የሚሰጡት ምክር በምንና በምን ጉዳይ ላይ የተመሠረተ እንደነበረ፣ በተለያዩ ጊዜያቶች የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ከሦስቱ የሀብተወልድ ልጆች ጋር በመነጋገር፣ የያዝኳቸውን ዋና ዋና ነጥቦች እንደሚከተለው አቀርባቸዋለሁ።

ሀ/ .... ወደፊት፣ ኢትዮጵያ የፈረንጆቹን ሥልጣኔ ለመቀበል የምትችለው፣ ከንጉሥ ጭቆናና አስተዳደርና ከመኳንንት ገዥነት ስትላቀቅ ነው። ....

ለ/ .... መኳንንትና የመኳንንት ወገኖች ዘመናዊውን ትምህርት አንማርም በማለታቸው፣ ለድሆች ልጆች ጥሩ ዕድል ከፍተዋል። ....

ሐ/ .... የድሆች ልጆች ጠንክረው ከተማሩ፣ በዕውቀታቸው የአስተዳደሩን ሥልጣን ወስደው የኢትዮጵያን ሕይወት ማሻሻል ይችላሉ።

መ/ .... ወደፊት የመኳንንት ወገን ሳይማር እንደዚሁ ከቀጠለ፣ የአባቱን ሀብት እንጂ፣ አባቱ ይዞት የነበረውን ሥልጣን አይወርስም። ....

ሠ/ .... የአልጋወራሽ ተፈሪ መኰንን አመራር ብዙ ተስፋ የሚሰጥ ነው። በዚህ አኳኋን ከቀጠለ፣ ኢትዮጵያ ከጨለማ ወደ ብርሃን ለመሸጋገር ዕድል አላት ...

መኰንን ሀብተወልድ ለወንድሞቻቸው ባዘጋጁት የምክር መስጫ ፕሮግራም፣ በቅደም ተከተል የሚያደርጓቸው ንግግሮች ከዚህ በላይ በተዘረዘሩት በአምስቱ ዋና ዋና ነጥቦች ላይ የተመሠረቱ ሲሆኑ፣ በየጊዜው የገለጿቸው

አስተያየቶች ሁሉ በአንድነት ተደምረውና ተዋህደው ፍሬ ነገሮቹ ቢጨመቁ፣ ከዚህ በታች የቀረቡትን አጠቃላይ ሐሳቦች ሊሰጡ ይችላሉ።

« .... የወደፊቷ ኢትዮጵያ የሥልጣኔውን መንገድ ለመከተልና የሕዝቦቿን ኑሮ ለማሻሻል የምትችለው፣ ከገባር ጭቆና አስተዳደር ስትላቀቅና መኳንንት አለአግባብ የሚጠቀሙበትን ሥልጣን፣ የሕዝብ ተቆርቋሪዎች ለሆኑት የድሆች ወገኖች በሰላም አስረክበው ሲወጡ ነው። ለአገር አስተዳደር አስፈላጊው ዕውቀት ላላቸው ለሕዝብ ወገኖች ሥልጣን መሰጠት አለበት ሲባል፣ መኳንንትን ለማጥፋት የሚያመለክት ጭራ መስሎ እንዳይገመት መጠንቀቅ ያስፈልጋል። መኳንንት ከነቤተሰቦቻቸውና ከነሀብታቸው በሰላም የመኖር መብታቸው መከበር አለበት። ነገር ግን ሥልጣንና ሀብትን በአንድነት አጣምረው በሕዝብ ጉዳይ ላይ ፈላጭ ቆራጭ መሆን አይገባቸውም። እኛ የምንቃወመው ይኸንን ነው። ስለዚህ፣ የድሆች ወገኖች በዘመናዊ ትምህርት ታንፀው፣ በዕውቀት መኳንንትን በልጠው ሥልጣን ለመቀበል ዝግጁ መሆን አለባቸው። እናንተም የሀብተወልድ ልጆች፣ የድሀው ሕዝብ ወገን ስለሆናችሁ፣ ለአገር አስተዳደር ተካፋይ ለመሆን ዕድላችሁ ሰፊ ነው።

የአገራችን መኳንንትና የመኳንንት ቤተሰብ የሆኑት ሁሉ፣ "ዕውቀትን ተጐናጽፈን የተወለድን" ስለሆነ፣ ለኛ ትምህርት አያስፈልገንም ብለው መከዳቸውን ተደግፈው ቁጭ ብለዋል። ነገር ግን ተወደደም ተጠላም፣ የወደፊቷ ኢትዮጵያ ወደ ፈረንጆቹ ሥልጣኔ ማምራት ግዴታዋ ስለሆነ፣ የተማሩና ለሕዝብ የሚያስቡ ሰዎች ያስፈልጓታል። እነዚህም ሰዎች የሚመረጡት እናንተን ከመሳሰሉት ተማሪዎች ውስጥ ነው። እኔ ይህን ሁሉ ስነግራችሁ፣ መኳንንትን ይጠላል ብላችሁ ታስቡ ይሆናል። አዎን ! መኳንንት ነኝ ብሎ የሚመጻደቀውን አልወድም። ነገር ግን መኳንንት ሆኖ ሕዝብ የሚያከብርና ለሕዝብ የሚያስብ ከሆነ አልጠላውም። እኔ የምጠላው፣ በመኳንንትነቱ ሳይሆን በአድራጐቱ ነው። "ሀብቱ የእኔ፣ ሥልጣኑም የእኔ፣" ብሎ በሕዝብ ላይ ፍርድ እያጓደለ የሚፈጽመውን ግፍ እያየሁ፣ እጅግ አዝናለሁ። እጅግም እበሳጫለሁ። መቸም ፈጣሪያችን አገራችንን ስለሚጠብቃት፣ የአልጋ ወራሽ ተፈሪ መኰንን አመራርና ያላቸው ፍላጐት፣ ከጨለማው ወደ ብርሃን ሊያሸግራት ይችላል የሚል ዕምነት አለኝ። በአልጋ ወራሽ ተፈሪ ላይ ያየሁት ትልቁ ቁም ነገር፣ ዘመናዊ ትምህርትን ለማስፋፋትና የሕዝቡን ልጆች ለማስተማር ቆርጠው መነሣታቸው ነው። እኔ እንኳ በአቅሜ እናንተን ከባላገር አውጥቼ ለማስተማር ከእናታችን ጋር ያንን ሁሉ ትግል ያደረግሁት፣ የአልጋ ወራሽ አመራርና የወደፊት ዕቅድ ብዙ ተስፋ ስለአሳደረብኝ ነው።

መኮብብ፣ አካለወርቅና አክሊሉ በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ትምህርታቸውን እስከፈጸሙበት ጊዜ ድረስ፣ አባት ሆነው ካሳደጓቸው ወንድማቸው ከአቶ መኰንን ሀብተ ወልድ በየወሩ የሚሰጣቸው ምክር አስተሳሰቡም ሆነ መንፈሱ ከዚህ በላይ በተገለጸው አኳኋን እንደነበረ፣ ሦስቱም በሕይወት ዘመናቸው ሊያስታውሱት ኖረዋል።

## ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ፈረንጅ አገር

መኰንን ሀብተወልድ እንደ ተመኙትና እንደ ደከሙበት ከ1912 ዓ.ም እስከ 1919 ዓ.ም ድረስ ለሰባት ዓመታት በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ሲማሩ የቆዩት ሦስቱ ወንድሞቻቸው፣ (መኮብብ፣ አካለወርቅ፣ አክሊሉ) የመጀመሪያውን ደረጃ

ትምህርት ፈጽመው ወደ ፈረንጅ አገር እንዲላኩ ከተመረጡት ወጣቶች መካከል ሆነው ቀረቡላቸው።

ህዳር 21 ቀን 1919 ዓ.ም፣ አልጋ ወራሽ ራስ ተፈሪ መኰንን እነዚህን ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ውጭ አገር የሚላኩትን ሠላሳ ሦስት (33) ተማሪዎች ሲያሰናብቱ በተደረገው ሥነ ሥርዓት ላይ፤ ከወላጆች ጋር ተካፋይ የሆኑት መኰንን ሀብተወልድ፣ ከደስታቸው ብዛት ከዓይናቸው የሚወርደውን እንባ ማገድ አቅቷቸው እንደነበረ ወንድሞቻቸው በሕይወታቸው ዘመን ሲያስታውሱት ኖረዋል። መኰንን ሀብተወልድ ፊታቸው በእንባ እየራሰ የገለጹት የደስታ ስሜት፤ ከብዙ ሁኔታዎች ጋር የተያያዘ መሆኑን መገንዘብ ይቻላል። ለሰባት ዓመታት ባለማቋረጥ ወንድሞቻቸውን እያተጉ በማስተማር ከዚህ ደረጃ በማድረሳቸው፤ የመጀመሪያው ትልቁ ደስታቸው መሆኑ አያጠራጥርም። ቀጥሎ ደግሞ እነዚህ ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ፈረንጅ አገር ለመሄድ የተመረጡት ሠላሳ ሦስት (33) ወጣቶች በሙሉ፤ እሳቸው እንደ ተመኙት ከትምህርታቸው በስተቀር ሌላ ወገን የሌላቸው የሕዝብ ልጆች በመሆናቸው፤ እጅግ አድርጎ አርክቷቸዋል። ቀደም ሲል እንደተገለጸው በመኰንን ሀብተወልድ ዕምነት፤ ራስ ተፈሪ መኰንን ሀገራቸውን ወደ ሥልጣኔ ለማሻገር ለሚያደርጉት ከፍተኛ ጥረት፤ ረዳቶቻቸውና ታማኞቻቸው መሆን የሚችሉት፤ እነዚህ የእገሌ ዘር ... የእገሌ ወገን ... የማይባሉት የሕዝብ ልጆች ናቸው።

አልጋወራሽ ተፈሪም አስተሳሰባቸው በዚህ መንፈስ ላይ የተመሠረተ ስለሆነ፤ እነዚህን ወጣቶች ሲያሰናብቱ፤ « ..... እኔ ሰው ነኝ ሟች ነኝ። ለማትሞተው አገራችን ቁም ነገር ይዛችሁላት እንድትመለሱ፣ እግዚአብሔርን እለምንላችኋለሁ። .... » ሲሉ የተናገሩት ቃል፣ ተማሪዎቹን ምን ያህል ኃላፊነት እንደጣሉባቸውና ተስፋ እንዳደረጉባቸው ያሳያል።

« ..... ዓለምን ያዳነ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ደቀመዛሙርቱን የመረጠው፤ ከታናናሽ ወገን እንጂ ከታላላቆቹ አልነበረም።... እነሆ እርስዎም ልዑል አልጋወራሻችን ኢትዮጵያን ከጨለማ ወደ ብርሃን ለማሻገር፤ ረዳቶችዎ እንድንሆን የመረጡንን ደቀመዛሙርት ፍሬያችንን ለማየት እንዲያበቃዎ አምላክን እንለምነዋለን። .... » ሲል በተማሪዎቹ ስም ሞገስ ወልደዮሐንስ ያደረገው ንግግር፤ የራስ ተፈሪን ትክክለኛ መንፈስ የሚገልጽ ስለሆነ፤ ለመኰንን ሀብተወልድና ለመሰሎቻቸው ሁሉ፤ ከዚህ የበለጠ ደስታ ሊሰማቸውና ከዚህ የበለጠ ተስፋ ሊያድርባቸው አይችልም።

## <u>አልጋወራሽ ካዘዙ፣ እኔ ምን እጨምርበታለሁ?</u>

**እማሆይ ያደግድጉ**

ሦስቱ የሀብተወልድ ልጆች ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ፈረንጅ አገር ከመጓዛቸው በፊት በምንኩስና ሕይወት ላይ የሚገኙትን እናታቸውን እማሆይ ያደግድጉን እንዲሰናበቱ፤ ህዳር 23 ቀን 1919 ዓ.ም መኰንን ሀብተወልድ ይዘዋቸው "ደንቢ" ሄዱ። እነዚህ ልጆች፤ ወደ ፈረንጅ አገር ለትምህርት መሄዳቸው ስለሆነ፣ መርቀው ያሰናብቷቸው ብዬ ስናገር፣ እናቴን አሳዝናቸው ይሆናል በማለት መኰንን ሀብተወልድ ስለፈሩ፤ ዋና ደጋፊያቸው የሆኑት የቤተሰቡ ንስሐ አባት መምሬ ገብረዮሐንስ፤ ከእማሆይ ያደግድጉ አጠገብ እንዲገኙ አስቀድመው አዘጋጁ።

ልጆቹ የተናፈቁ እናታቸውን አግኝተው ምሳ ከተበላ በኋላ፣ እማሆይ ፊታቸውን ወደ መኰንን መለስ አድርገው፣ ታዲያስ ? ...የነዚህ ልጆች ትምህርት የት ላይ ደረሰ ? ... ተገባደደ ? ወይስ ገና ብዙ ይቀራቸዋል ? ... ሲሉ ጠየቁ። አቶ መኰንን ቀደም ብለው መልሱን አዘጋጅተዋል። « ስለ ልጆቹ ትምህርት ዛሬ ልነግርዎ የመጣሁት፣ በጣም ደስ የሚያሰኝና የሚያኮራ ነገር ነው። አልጋወራሽ ልዑል ራስ ተፈሪ መኰንን፣ እነዚህ ልጆችዎ በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ለሰባት ዓመታት በትጋት ተምረው የፈጸሙትን የፈረንሣይ ትምህርት ተመልክተው፣ ከዚሁም ከፈረንጁ ትምህርት ጋር አጣምረው ሲያጠኑት የነበረውን ዋናውን የአገራችንን ትምህርት አይተው፣ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክሳዊ ሃይማኖታችን አባት መንበር ከሆነውና፣ ኢየሩሳሌም አጠገብ ወደሚገኘው ወደ እስክንድርያ ተማሪ ቤት ሄደው፣ የሊቃውንቶች ትምህርት እንዲማሩ አዘዋል። እኔም ይህንኑ ትዕዛዝ ተቀብዬ፣ ልጆቹ በመሬት ባቡር ጉዞአቸውን ከመጀመራቸው በፊት፣ እናታችን መርቀው እንዲያሰናብቷቸው አልጋወራሽን አስፈቅጄ ይዤአቸው መጥቻለሁ። » አሏቸው። ወዲያውም የንስሐ አባት መምሬ ገብረዮሐንስ ተነሥተው፣ « .... አቶ መኰንን እንደነገረኝ እነዚህ ልጆቻችን ለከፍተኛ ዕውቀት በአልጋወራሽ ትዕዛዝ የሚላኩበት እስክንድርያ የተባለው አገር፣ ከብዙ ዘመናት በፊት፣ እነ አባ ፍሬምናጦስ፣ እነ አባ ማቲያስ፣ የተማሩበት ስለሆነ በውነቱ ልጆቻችን ላጋጠማቸው ይህን የመሰለ ትልቅ ዕድል፣ ከዚህ የበለጠ ደስታ ሲኖረን አይችልም .... » አሉ።

መኰንን ሀብተወልድና መምሬ ገብረዮሐንስ በቅድሚያ ተስማምተው ይህን የመሰለውን ዲስኩር ያደረጉት፣ የእማሆይ ያደግድጉን መንፈስ ለመማረክ መሆኑ ለማንም ግልጽ ነው። ይሁን እንጂ የተፈጥሮ ብልህነትና አስተዋይነት ያላቸው መነኩሲት የሰጡት መልስ፣ የተነገራቸውን ሁሉ ከልባቸው አምነው የተቀበሉት አይመስልም። « ... ጌታችን አልጋወራሽ በዚያ ሁሉ ከባድ ሥራቸው ላይ ለእኔ ለአልባሌዋ[*] ልጆች በማሰብ፣ ወደ ፈረንጅ አገር ሄደው የፈረንጅ ትምህርት እንዲማሩ ያዘዙት እሳቸው ከሆኑ፣ እኔ ምን እጨምርበታለሁ? .... እግዚአብሔር በደህና ጠብቆ በሰላም ወስዶ እንዲመልሳቸው ከመጸለይ በስተቀር በእኔ በኩል የሚደረግ ነገር የለም። .... » ካሉ በኋላ ፊታቸውን ወደ ንስሐ አባታቸው መለስ አድርገው፣ « ... አባቴ አሁን ሲናገሩ፣ መኰንን ያስጠናዎትን አስታውሰው፣ ልጆቻችን የሚሄዱት ታላላቆቹ ጻድቃኖች ወደተማሩበት አገር ስለሆነ፣ መደሰት አለብን ብለዋል። እንደእኔ እንደ መኃይሟ ሐሳብ ከሆነ ደስታ በጅምሩ ላይ ከሚሆን፣ መጨረሻው ምን እንደሚሆን ሲታይ ይሻላል። .... » ካሉ በኋላ ፊታቸውን ወደ ልጆቻቸው መልሰው፣ « ... እናንተ ልጆች ! ይኸው የፈረንጅ ትምህርት ለመማር ወደ ፈረንጅ አገር እንድትሄዱ ታዛችኋል ተብሏል። ፈረንጅ አገር ሄዳችሁ ምን ተምራችሁ፣ ምን መስላችሁ እንደምትመለሱ ባላውቅም፣ በምትኖሩበት አገር ሁሉ የሃይማኖታችንን ጉዳይ በቅጡ እንድታስቡበት አጥብቄ አደራ እላችኋለሁ። ወንድማችሁ መኰንን በቶሎ እንደምትሄዱ ሲነግረኝ፣ ትምህርታችሁ ምን ያህል ጊዜ እንደሚያቆያችሁ አልገለጸልኝም። ስትመለሱ፣ ምናልባት ልታገኙኝ ወይም ላታገኙኝ ትችላላችሁ። ትልቁ ቁም ነገር የኔ መኖርና አለመኖር አይደለም። እንደተመለሳችሁ፣ ለደጉና ለታዋቂው አባታችሁ ለአለቃ ሀብተወልድ ስም ማስጠሪያና መታሰቢያ ሆኖ የሚኖር፣ በደብረ ኃይል ራጉኤል አንድ ነገር እንድታቆሙላቸው እለምናችኋለሁ። ትንንሾች ልጆች በነበራችሁበት ጊዜ እንደምጨቀጭቃችሁ፣ የራጉኤል ደብራችንን እንደአባታችሁ አገልግሉ

[*] በዚያን ጊዜ አቶ መኰንን የርሻና የመሥሪያ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ነበሩ።

[*] የማይታወቁ ... ያልታወቁ



የሀብተወልድ ልጆች ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ውጭ አገር ሲላኩ፤
ከግራ ወደ ቀኝ የቆሙት አክሊሉና መክብብ ሲሆኑ ወንበር የያዙት አካለወርቅ ናቸው፤

አልላችሁም። ዛሬ ጊዜው ተለውጧል። እናንተም ተለውጣችኋል። ግን፣ አንድ መታሰቢያ የሚሆን ቋሚ ነገር መሥራት አያቅታችሁም እላለሁ። …. » በሚል ቃል እማሆይ ያደግድጉ ልጆቹን አሰናበቷቸው።

በዘመነ ሉቃስ በኅዳር ወር 1919 ዓ.ም እነዚህ የሀብተወልድ ልጆች የሚገኙበት ሠላሳ ሦስት (33) ተማሪዎች በአንድነት ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ውጭ አገር ሲላኩ፣ ከወጣቶቹ ወላጆች አብዛኛዎቹ፣ በአልጋወራሽ ራስ ተፈሪ ላይ ምን ያህል ቅሬታ እንዳሳደሩና ምን ያህል እንዳዘኑ፣ በዚያን ጊዜ የነበሩት ሰዎች ሁሉ ሲያስታውሱት ኖረዋል። የቤተሰቡ ተቃውሞ፣ ለሥልጣኔ ትምህርት እየተባለ ወደ ፈረንጅ አገር የሚላኩት ልጆቻችን ሃይማኖታቸውን ይለውጣሉ በሚል አስተሳሰብ ስለሆነ፣ ይህ ሥጋት መሠረት የሌለው መሆኑን አስረድቶ የትምህርትን ጠቃሚነት ለማሳመን የተደረገው ጥረት ሁሉ ሙሉ በሙሉ ተቀባይነት ሳያገኝ ቀረ። አንዳንዶቹ ቤተሰቦችም፣ ለከፍተኛ ትምህርት የተመረጡ ልጆቻቸውን አስረው፣ ከጉዞአቸው ለማስቀረት ብዙ ሙከራ አድርገው ነበር። በተለይም በጣም አስደንጋጭ ሆኖ ሲተረክበት የነበረው የሁለቱ ተማሪዎች፣ የመሸሻና የአርዓያ ሥላሴ አባት የሆኑት ቀኛዝማች ኃይሌ ኪዳነወልድ፣ ልጆቻቸው እንዳይሄዱ ለማስቀረት የወጠኑት የጭካኔ ዕቅድ ነው። ቀኛዝማች ኃይሌ፣ የሁለቱ ልጆቻቸውና የሌሎቹም ጓደኞቻቸው ወደ ፈረንጅ አገር መሄድ፣ በትምህርት ሳቢያ የኦርቶዶክስ ሃይማኖታቸውን የሚያስለውጥና ወደ ካቶሊክ ዕምነት የሚያስጠምቅ ነው ብለው ከልባቸው ስለአመኑበት፣ አእምሮአቸው በትክክል ማሰቡን እንዲስት አስደርጉታል። ስለዚህ፣ ልጆቹ እዚህ ወጥመድ ውስጥ ገብተው ወላጆቻቸውንና አገራቸውን ከባድ ኃዘን ላይ ከሚጥሉ፣ ባሕር ሳይሻገሩ አገራቸው መሬት ላይ ሞተው ብንቀብራቸው ይሻላል በማለት፣ ልጆቹ የተሳፈሩበት ባቡር ከአዲስ አበባ ተነሥቶ ጉዞውን እንደ ጀመረ፣ አቃቂ ላይ የሐዲዱን መስመር ቆርጠው ባቡሩን ለመገልበጥና ሁሉም እንዲያልቁ ለማድረግ ከባድ ውሳኔ አደረጉ። ቀኛዝማች ኃይሌ፣ ይህንን ያሰቡትን ለመፈጸም ሰዎቻቸውን አስከትለው በሰጋር በቅሎ እየገሰገሡ አቃቂ ሲደርሱ፣ በምሥጢር ያዘጋጁት አደጋ ቀደም ብሎ በፀጥታ ጠባቂዎች ተደርሶበት ስለነበረ፣ አንዳች እርምጃ ሳይወስዱ ወዲያውኑ ተያዙ።*

ወደነበርንበት የታሪክ ምዕራፍ ስንመለስ፣ የሀብተወልድ ልጆች እናት ይቶት ያደግድጉ፣ ምንም እንኳ ወንዶቹ ልጆቻቸው እንደ አባታቸው የራጉኤል አገልጋዮች በመሆን ፋንታ ወደ ፈረንጅ ትምህርት በመዝለቃቸው ቢያዝኑም፣ አልጋወራሽ ተፈሪ አዘዋል ስለተባለ፣ መርቀው አሰናብተዋቸዋል። በስንብቱ መጨረሻ ላይ ከምትሄዱበት አገር ስትመለሱ፣ እኔን ልታገኙኝ ወይም ላታገኙኝ ትችላላችሁ። የሚል ቃል በመወርወራቸው፣ በልጆቹ አዕምሮና በተለይም በአቶ መኰንን ላይ ተቀርጾ ቀርቶ ነበር። እናታቸው የመጨረሻ ሕይወታቸውን በተሟላ ደስታ እንዲያሳልፉ የመኰንን ሀብተወልድ ጥልቅ ምኞት ስለሆነ፣ በ1922 ዓ.ም የገንዘብ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር በነበሩበት ጊዜ፣ " አቢሲኒያ " የተባለውን ባንክ ከእንግሊዞች ማህበር ላይ ለመግዛት ተልከው ወደ ካይሮ ሲሄዱ፣ እግረ መንገዳቸውን እናታቸውን ኢየሩሳሌም ወስደው ካሳለሟቸው በኋላ፣ የተናፈቁ ልጆቻቸውም ከእስክንድርያ ካይሮ መጥተው እንዲያይዋቸው አደረጉ። በኢየሩሳሌም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የተወለደበትን ቤተልሔምንና ያደገበትን ናዝሬትን፣ የተጠመቀበትን ዮርዳኖስንና፣ ታምራት የፈጸመበትን ቃና ዘገሊላን እየተዘዋወሩ

* ታሪኩን ለደራሲው የገለጹት፣ መኰብብ ዳምጤ፣ አካለወርቅ ሀብተወልድ፣ ጌታሁን ተሰማ፣ እና ሌሎቹም ናቸው።

በመሳለማቸው፣ እማሆይ ያደግድጉ የተሰማቸውን ደስታ መለካት አልተቻለም። ቀደም ሲል፣ ይቶት ያደግድጉ አንጋፋው ልጃቸው መኰንን ሀብተወልድ ልቡ ወደ ከተማ ሕይወትና ወደ ፈረንጅ ጉዳይ ተመርቶ፣ የአባቱን ታላቅ ደብር ራጉኤልን ረስቷል በማለት፣ የያዙባቸውን ቅሬታ በሙሉ ከዚህ ከኢየሩሳሌም ጉብኝት በኋላ ሰርዘውላቸዋል። "ልጄ በአምላክ ፈቃድ የንጉሥ ባለሟል ለመሆን በቅተሃል። እነዚህ አባት ሆነህ ያሳደግካቸውም ልጆች፣ ያንተኑ ፈለግ ተከትለው ለወግ ለማዕረግ እንዲበቁ ሐሳብህን ፈጣሪያችን ይፈጽምልህ" ብለው መርቀዋቸዋል።

ከጠላት ወረራ በኋላ ነፃነት ሲመለስ፣ የእማሆይ ያደግድጉ ዋና ጸሎት በውጭ አገር የተበታተኑት ልጆቼ በሙሉ ተመልሰው ለማየት ያብቃኝ የሚል ነበር። ጦርነቱ ከመጀመሩ ከጥቂት ወራት በፊት ትምህርቱን ፈጽሞ ወደ አገሩ የተመለሰውን አካለወርቅን ብቻ ለማግኘት ሲችሉ፣ ሌሎቹን ስደተኛውን መኰንንን፣ ተማሪዎች የነበሩትንና ኋላም በስደት ከወንድማቸው ጋር የቀሩትን፣ መክብብንና አክሊሉን ለማየት ሳይታደሉ ቀሩ። ነፃነት ከተመለሰ ከጥቂት ጊዜ በኋላ፣ ሳይታሰብ በድንገት እማሆይ ያደግድጉ በተወለዱ በስድሳ አምስት (65) ዓመታቸው ከዚህ ዓለም በሞት ተለዩ።

## የመኰንን ሀብተወልድ የሥልጣን ዕድገት

ቀደም ሲል በምዕራፍ አንድ ላይ እንደተገለጸው፣ መኰንን ሀብተወልድ ከላጋር ጉምሩክ ወደ ዋናው የጉምሩክ መሥሪያ ቤት ተዛውረው የሒሳብ ሹም ከሆኑ በኋላ፣ የዋናውን ዲሬክተር የሙሴ ደልቢን አድናቆት በሰፊው አገኙ። የሚሰጣቸውን የሥራ መምሪያ፣ ቃል በቃል እየተከተሉ የሚያጠናቅቁ፣ የሥራቸውን ሰዓት የሚያከብሩ፣ የተፈጸሙትን ሥራዎች በመዝገብ የሚይዙ፣ ከጉምሩክ ቀረጥ ለመንግሥት የሚሰበሰበውን ገንዘብ ሒሳብ፣ በስታቲስቲክ እየለዩ የሚያቀርቡ በመሆናቸው፣ በጥቂት ወራቶች ውስጥ የሙሴ ደልቢን አድናቆት ብቻ ሳይሆን መታመንና መወደድንም አተረፉ።

ግብፃዊው ደልቢ፣ በእሱ መሪነት የሚካሄደው የጉምሩክ ዋና መሥሪያ ቤት ከማናቸውም የመንግሥት መሥሪያ ቤቶች ሁሉ፣ የቀለጠፈና በዘመናዊ አመራር የሚካሄድ ነው ብሎ ስለአመነ፣ አልጋወራሽ ራስ ተፈሪ መኰንን መጥተው እንዲጎበኙለት አስፈቅዶ ፕሮግራም አዘጋጀ። በዚህ መሠረት የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት አልጋ ወራሽ በመስከረም 1913 ዓ.ም ይህን የጉምሩክ ዋና መምሪያ ለመጐብኘት ከሥፍራው ሲደርሱ፣ ሙሴ ደልቢ ሠራተኞቹን አሰልፎ ያሸበረቀ አቀባበል አደረገላቸው። በጉብኝቱ ፕሮግራም ላይ ሙሴ ደልቢ ይህ መሥሪያ ቤት ለመንግሥቱ መተዳደሪያ ገቢ የደም ሥር ነው በማለት ገለጻ ከአደረገ በኋላ፣ ስለ ሥራው አመራር ሲያስረዳ፣ የመኰንን ሀብተወልድን ትጋትና የሥራ ጥራት ልዑል አልጋወራሹ እንዲመለከቱት አቀረበ። መኰንን፣ ከሰው ቀድሞ ሥራው ላይ የሚገኝ፣ ከሰው መጨረሻ ቢሮውን የሚለቅ፣ ተወዳዳሪ የሌለው ትጉህ ሠራተኛ መሆኑን ሙሴ ደልቢ ካስረዳ በኋላ፣ መኰንን በሒሳብ ሹምነቱ ከጉምሩክ የተገኘው የመንግሥት ገቢ፣ የየቀኑና የየሳምንቱ፣ የየወሩና የየዓመቱ ምን ያህል እንደሆነ በሰንጠረዥ የሠራውን አልጋወራሽ ሲመለከቱ፣ እሳቸውም ከፍ ያለ አድናቆት አደረባቸው። ወዲያውም ፊታቸውን ወደ መኰንን መልሰው አንዳንድ ጥያቄዎችን አቀረቡ።

አልጋወራሽ፤ የት ተወልደህ አደግህ ? እስከ ምን ድረስ ተምረሃል ?

መኰንን ሀብተወልድ፤ የተወለድኩት በአድዓ ወረዳ "ደንቢ" በተባለው ቀበሌ ነው። አባቴ አለቃ ሀብተወልድ የእንጦጦ ደብረኃይል ራጉኤል ታዋቂ ደብተራ የነበሩ ናቸው። እኔንም በዝቋላ ወንበር ማርያም፣ ዜማና ቅኔ ካስተማሩኝ በኋላ፤ በራጉኤል ዲቁና ተቀብዬ እንዳገለግል አደረጉ። ቀጥሎም ዳግማዊ አፄ ምኒልክ በታመሙ ጊዜ ከወንድሜ ከታከለ ወልደሐዋርያት ጋር ተመርጠን ድርሳን በመድገም በጠበል አጠማመቁ ሥርዓት ላይ አገልግያለሁ።

አልጋወራሽ፤ ታዲያ የራጉኤል አገልግሎትህን ለምን አቋረጥክ ? ....

መኰንን ሀብተወልድ፤ እንጦጦ በኖርኩበት ዘመን የአስም ሕመም ስለአደረብኝ፤ መጀመሪያ ወደ አሩሲ ቀጥሎም እዚሁ አዲስ አበባ ተዛውሬ መኖር ግዴታ ሆነብኝ።

አልጋወራሽ፤ ሒሳብ የት አጠናህ ?

መኰንን ሀብተወልድ፤ ለፍልውሃ መግቢያ ገንዘብ ተቀባይ ሆኜ ስሠራ፣ በትርፍ ጊዜዬ አሊያንስ ፍራንሴዝ እየተመላለስኩ፤ የአራት መደብ ሒሳብ ካጠናሁ በኋላ፣ የፈረንሣዊኛም ቋንቋ ተምሬ የተጻፈ ማንበብና መረዳት ችያለሁ።

አልጋወራሽ፤ ለምን እንዲህ ከሣህ ? ያምሃል ?

መኰንን ሀብተወልድ፤ ክሳቴ የተፈጥሮ ነው። ምግብ አልደፍርም። ቅባትና ሥጋ አልበላም። መጠጥ አልቀምስም። በተፈጥሮዬም ሥጉ ነኝ። በአንድ ሌሊት ከአራት፣ ቢበዛ ከአምስት ሰዓት በላይ መተኛት አልችልም።

አልጋወራሽ፤ አሁን ባሳየኸን የሒሳብ መግለጫ ከጉምሩክ የተገኘው ገቢ ባለፉት ጥቂት ወራቶች ውስጥ በጣም ማደጉን ያሳያል። ይኸ ከምን የተነሣ ነው ? .... እናንተ እንደፈለጋችሁ ታክሱን ከፍ በማድረግ የከፋዩን ወገን አልተጫናችሁትም ወይ ? ...

መኰንን ሀብተወልድ፤ እርግጥ ነው ! ካለፉት ጥቂት ወራቶች ጀምሮ በጠቅላላው ከባሕር ማዶ በሚመጡ ዕቃዎች ላይ ታክሱን በተገቢው መንገድ ጨምረናል። ልዑል ጌታችን እንደሚያውቁት፤ ከውጭ ተገዝተው በሚመጡ ዕቃዎች ላይ ታክስ መጨመሩ ኑሮውን ለማሻሻል ሌት ተቀን የሚደክሙትን ድሀውን ሕዝብዎን ጨርሶ አይነካውም። ጉዳዩ ቀጥታ የሚመለከታቸው ለሕይወታቸው ምቾት በመፈለግ ልዩ ልዩ የሉክስ ዕቃዎች ከፈረንጅ አገር የሚያስመጡትን ገንዘብ ያላቸውን ራስ ደጃዝማቾችን እና ሀብታም ነጋዴዎችን



አቶ መኰንን ሀብተወልድ የላጋር ጉምሩክ ዋና የሂሣብ ሹም፤

ነው። እነሱም ቢሆኑ ታክስ በመጨመሩ እስካሁን ወቀሳ ሲሰነዝሩ አልተሰማም። ከውጭ የሚያስመጧቸውንም ዕቃዎች እያስፋት ሄዱ እንጂ፣ በታክሱ ማደግ ምክንያት አልቀነሱም ። እንዲያውም በእኔ በትንሹ ሠራተኛ አስተያየት ታክሱ አሁንም እንደገና ተጠንቶ መጨመር ይኖርበታል።

አልጋወራሽ፤ ቅድም አለቃህም አንተም ስታስረዱን፤ ከጉምሩክ የሚገኘው ገቢ ለመንግሥታችን መተዳደሪያ እንደ ደም ሥር የሚቆጠር ነው ብላችኋል። ይህ የምትሉት ትክክል ከሆነ፤ የምታስከፍሉትን ታክስ ቶሎ ቶሎ በማሳደጋችሁ ዛሬ እንኳ ባይሆን፤ ነገ ዕቃ አስመጭዎችን አስመርሮ፤ ወደፊት ምንም ዓይነት ዕቃ እናስመጣም ቢሉ፤ ለመንግሥት የተመኛችሁትን ገቢ የሚቀንስባችሁ ሊሆን አይችልም ወይ ?

መኰንን ሀብተወልድ፤ በእኔ በትንሹ ሠራተኛ አስተያየት ፤ ባለጸጎቹ የሕይወታቸውን ምቾት አጥብቀው ስለሚወዱ፤ የጉምሩኩ ቀረጥ ምንም ቢጨምር፤ የሚፈልጓቸውን ዕቃዎች ከማስመጣት አይታገዱም። እዚህ ላይ ልዑል ጌታዬ ቢፈቅዱልኝ ፤ እኔ በዚህ በጉምሩክ ሥራ ላይ ከተሠማራሁበት ጊዜ ጀምሮ አንድ የሚሰማኝ ነገር አለ። የጉምሩክ ገቢ ምንም እንኳ በአሁኑ ሰዓት ለመንግሥት ማስተዳደሪያ እንደ ደም ሥር የሚቆጠር ነው እየተባለ ቢነገርም፤ በዚህ ዓይነት አሠራር መቀጠሉ ለዘለቄታው ልዑል ጌታዬ ለሚደክሙለት ሕዝብዎ ጠቃሚነቱ አልታየኝም።

አልጋወራሽ፤ በምን ምክንያት ?

መኰንን ሀብተወልድ፤ እኔ እንዳየሁት ከውጭ የሚመጡት ዕቃዎች ሁሉ፤ ለአንዳንድ የጤና መከላከያ ከሆኑት ጥቂቶች መድኃኒቶች በስተቀር፤ ከመቶ ዘጠና ዘጠኙ፤ ለባለጸጋዎቹ ሕይወት ምቾት የሚሰጡ ናቸው። አንዳንዶቹን ዕቃዎች ለምሳሌ ያህል ብንጠቅሳቸው፤ ከሐር የተሠሩ ጨርቃጨርቆች፤ ጫማዎች፤ የብርድ መከላከያ የሱፍ ልብሶች፤ ከወርቅና ከአልማዝ የተሠሩ ጌጣጌጦች፤ የኪስና የእጅ ሰዓቶች፤ ከመጠጦችም ሻምፓኝ፤ መደቅሳ ኮኛክና ፈርኔት ብራንካ፤ ልዩ ልዩ ሽቶዎችና የፀጉር ቅባቶች ወዘተ .... ናቸው። ባለጸጋዎቹ እነዚህን የመሳሰሉትን ዕቃዎች ከባሕር ማዶ ለማስመጣት የሚችሉት፤ መንግሥታችን የወርቅ ዋስትና ባለው የውጭ አገር ገንዘብ እየከፈለላቸው ነው። እነሱ ግን ለመንግሥታችን ገቢ የሚያደርጉት በአገራችን ውስጥ ያመረቱትን ገንዘብ ነው። ስለዚህ፤ በአንድ በኩል ከጉምሩክ ቀረጥ የሚገኘው ገቢ የሚያጓጓ መስሎ ቢታይም፤ በሌላ ወገን ደግሞ የመንግሥታችን የወርቅ ሀብት ለጥቂቶች

ሀብታሞች ምቾት ወጭ መሆኑ ለዘለቄታው ጉዳት ይመስለኛል። ስለዚህ፤ የሀገራችን የወርቅ ሀብት ይህን ለመሳሰለ ወጭ እንዳይውል ቢቆጠብ፤ ልዑል ጌታችን ኢትዮጵያን ለማሠልጠን ባለም ሰፊ ዕቅድ፤ ለምሳሌ እንደ ጨርቃ ጨርቅ ፣ እንደ ሳሙና እና እንደ ምስማር የመሳሰሉትን ጥቃቅን ፋብሪካዎች ለማቋቋም የሚጠቅም ይሆናል ብዬ አስባለሁ።

አልጋወራሽ፤ ስለመኳንንትና ስለ ባለጸጎች ኑሮ ስትናገር ቂምና ጥላቻ ያለህ ይመስላል። በተለይ የደረሰብህ በደል አለ ?

መኰንን ሀብተወልድ፤ እኔ ለልዑል ጌታዬ የምናገረው የማስበውን ብቻ ነው። በመኳንንት ሆነ በባለጸጎች ላይ ቂምም ጥላቻም የለኝም። በራሴም ላይ በቀጥታ ያደረሱብኝ በደል የለም። ነገር ግን ልዑል ጌታችን ኢትዮጵያን ወደ ሥልጣኔ ለማሻገር ያለ ዕረፍት ብዙ ጥረት ሲያደርጉ፤መኳንንት ሁሉ የየራሳቸውን ሕይወት ለማመቻቸት እንጂ፤ በምንም ጉዳይ ተካፋዮች ሆነው ባለመታየታቸው ቅር ይለኛል። ይኸም የኔ የግል አመለካከት ነው።

አልጋወራሽ፤ አንተ በተለየ አኳኋን የምትመለከታቸው እነዚህ ሰዎች፣ እኛ አገራችንን ለማሻሻል በምናደርገው ሙከራ በምን መንገድ ሊረዱን ይችሉ ነበር ?

መኰንን ሀብተወልድ፤ የቀረው ቢቀር ለሥልጣኔ መሠረት የሆነውን ዘመናዊ ትምህርት ለማስፋፋት ልዑል ጌታዬ የግል ገንዘብዎን ጭምር እያወጡ ሲደክሙ፤ መኳንንትና ባለጸጐች ለምን ተካፋይ አይሆኑም ? .... ሕዝብ ይህንን አተኩሮ የሚመለከት ይመስለኛል።

አልጋወራሽ፤ የምታስበውንና የሚመስልህን ሁሉ ሳታመነታ ገልጠህ መናገርህ እውነተኛ ሰው መሆንህን ያመለክታል። ሐሳብህን ተረድተነዋል። ወደፊት እንደአስፈላጊነቱ እናነጋግርሃለን። ትጋትህን ቀጥል ! .... ›› በሚል ቃል ልዑል አልጋወራሽ የመኰንን ሀብተወልድን ሞራል በጣም ከፍ አድርገው፤ የጉምሩክ ጉብኝታቸውን ፈጸሙ።

## ያልታሰመ ሹመት በድንገት

ራስ ተፈሪ መኰንን የጉምሩክን ዋና መሥሪያ ቤት ከጐበኙ ከሁለት ሳምንት በኋላ ዋናው ዲሬክተር ሙሴ ደልቢ በሁለት ዝግ እንቬሎፖች የተላኩ ሁለት ደብዳቤዎች ደረሱት። አንደኛው ከጽሕፈት ሚኒስቴር የተላከ ሲሆን ሁለተኛው ‹‹ ብርቱ ምሥጢርና እጅግ አስቸኳይ ›› የሚል ነበር። እንደተለመደው ሙሴ ደልቢ ጸሐፊውን ጠርቶ በመጀመሪያ ይህን ብርቱ ምሥጢር የሚለውን ከጽሕፈት ሚኒስቴሩ ደብዳቤ አስቀድሞ እንዲያነብለት አዘዘው። በደልቢ አስተያየት፤ ከጽሕፈት ሚኒስቴር የመጣው ደብዳቤ ያለጥርጥር ለአንዳንድ ራሶችና

ደጃዝማቾች የሚፈቀድ የቀረጥ ነፃ ጉዳይ ነው በማለት ቁምነገር አልሰጠውም። ብርቱ ምሥጢር በሚል ርዕስ ደብዳቤውን የጻፈው፣ በጉምሩኩ ዋና መሥሪያ ቤት የአስተዳደር ኃላፊ የሆነ ሰው ነው። « .... እርስዎ ከመሬት አንሥተው የሒሳብ ሹም አድርገው የሚያንቀባርሩት መኰንን ሀብተወልድ፤ የርስዎን የደጉን ጌታዬን ሥራ እያጥላላ እርስዎን ለማሻር የተንኮል አድማ ሲጠነስስ ደርሼበታለሁ። እኔንም ትሁት ታዛዥዎን ከእሱ ጋር እንድሆን ያለማቋረጥ ይለምነኛል። ዋና ሐሳቡ፤ አድማ ተደርጐ ሁላችንም የምንፈርምበት ደብዳቤ ለአልጋ ወራሽ ተጽፎ እርስዎን ለማሻርና በምትክዎ ሌላ ግብፅ ያልሆነ ኢትዮጵያዊ ለማሾም ነው። እኔ በዚህ ሐሳብ አልስማማም ብዬ ሞግቼዋለሁ። ከመኰንን ጋር የማልስማማበትም ዋናው ምክንያቱ፤ እርስዎ ደጉ ጌታዬ መሥሪያ ቤታችንን እንደ ፈረንጅ አገር መሥሪያ ቤት ለማድረግ የሚያደርጉትን ድካምና ለኛም ለሠራተኞችዎ ያሳዩትን ደግነት ደህና አድርጌ ስለማውቅና ስለማምንበት ነው። ስለዚህ ያደረጉለትን ታላቅ ውለታ ረስቶ ጠላትዎ ከሆነው ከዚህ ሰው እንዲጠነቀቁ አደራ እልዎታለሁ። ..... »

ሙሴ ደልቢ በዚህ በደረሰው ደብዳቤ በጣም ተናደደ። በጣምም አዘነ። ለካስ እኔ የማሳድገው ዋናውን ጠላቴን ኖርዋል። አንድ መንገድ ፈልጌ ከሥራው ነቅዬ እጥለዋለሁ ካለ በኋላ፤ ሁለተኛውን ከጽሕፈት ሚኒስቴር የመጣለትን ደብዳቤ እንዲያነብ ጸሐፊውን አዘዘ። « .... ይድረስ ለሙሴ ደልቢ፤ እርስዎ በሚመሩት መሥሪያ ቤት የሒሳብ ሹም የሆነው አቶ መኰንን ሀብተወልድ፤ በልዑል ራስ ተፈሪ መኰንን የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴና አልጋወራሽ ፈቃድ የአገር ግዛት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ ሆኖ እንዲሠራ ስለተወሰነ፤ በምትኩ ለጉምሩክ ዋና መሥሪያ ቤት ሒሳብ ሹም የሚሆን በአስቸኳይ እንዲመድቡ መታዘዙን አስታውቃለሁ። .... »

ፊርማ ቀኛዝማች ደሀኔ ወልደማርያም
የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር

ክቡር ደልቢ ይህን ሲሰማ በድንጋጤ የሚያደርገው ጨነቀው። ማንም ሳይጠይቀው እሱው ራሱ አስቦ መኰንን ሀብተወልድን እንደዚያ ክቦ ከአልጋወራሽ ተፈሪ ጋር ማስተዋወቁ፣ ስሕተት ነው የሚል ቁጭት አደረበት። ሆኖም በዚህ ጉዳይ የአልጋወራሽን ትዕዛዝ በአክብሮት ከመቀበል በስተቀር ምንም ማድረግ እንደማይችል ተገነዘበ። ይልቁንም ከእንግዲህ ወዲህ ይህን ሰው በወዳጅነት አጥብቄ ካልያዝኩት፤ በአገር ግዛት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊነቱ ነገር ጠምጥሞ ሊያስጠቃኝ ወይም የውጭ ዜጋ በመሆኔ ከአገር ሊያስወጣኝ ይችል ይሆናል የሚል ሥጋት ሳያድርበት አልቀረም። ምን ማድረግ እንደሚሻለው ሲያወጣና ሲያወርድ፤ መኰንን ሀብተወልድ በሊጋባው በኩል ቤተመንግሥት ተጠርተው አዲሱ ሹመታቸውን በወግ ከተቀበሉ በኋላ፤ በቀጥታ ወደ አለቃቸው ቢሮ ሄደው ስሜታቸውን ገለጹ። « .... እኔ ዛሬ በልዑል አልጋወራሽ ለዚህ ከፍተኛ ሥራ የታጨሁት በርስዎ ነው። ገና ከመጀመሪያው ፍልውሃ ገንዘብ ተቀባይ ሆኜ ስሠራ፤ በዕረፍቴ ጊዜ እየተማርኩ ራሴን እንዳሻሽል ያደረጉልኝን እርዳታና ማበረታቻ ምንጊዜም አልዘነጋውም። ቀጥሎም በሒሳብ ሥራ ከተቀጠርኩበት ከላጋር ጉምሩክ ወደዚህ ወደ ዋናው መሥሪያ ቤት ተዛውሬ የሒሳብ ሹም እንድሆን ከባዱን ኃላፊነት የሰጡኝ እርስዎ ነዎት። በመጨረሻም ስለሥራዬ ጥራትና ስለ ትጋቴ ለልዑል አልጋወራሽ አቅርበው በማስረዳትዎ፤ ዛሬ ይህንን ከፍተኛ ኃላፊነት ለመቀበል በቅቻለሁ። ልዑል ጌታችን አልጋወራሽ ይህንን እርምጃ የወሰዱት በርስዎ ላይ

ሙሉ ዕምነት በማሳደራቸው ነው። ይኸውም እርስዎ ሰውን አትግተውና አስተምረው ባጭር ጊዜ ውስጥ ለኃላፊነት ለማብቃት የተለየ ጥበብ ያለዎት ስለሆነ፤ በእኔ ምትክ ችሎታ ያለው ሰው ለመመደብ አይቸገሩም ብለው ስለአሰቡ ነው። እንግዲህ የኔ ዕድል በሩ የተከፈተው በርስዎ ስለሆነ፤ ጥልቅ ምስጋናዬን ከማቅረብ በስተቀር ሌላ የምጨምረው የለም። .... » መኮንን ሀብተወልድ ያደረጉት ንግግር፤ የሙሴ ደልቢን መንፈስ ስለማረከ፤ ከወንበሩ ብድግ ብሎ የእጅ ሰላምታ በመስጠት የጋለ ደስታውን ከገለጸላቸው በኋላ፤ ያ በመኮንን ላይ ወንጀል ተጽፎ የቀረበለትን ደብዳቤ፤ እኔ አላመንኩበትም ሆኖም ብታነበው የተገባ ነው ብሎ ሰጣቸው። አቶ መኮንን፤ የተጻፈውን አንብበው ከተረዱ በኋላ፤ « .... እንግዲህ ይህን የደረስዎትን መረጃ እስከ መጨረሻው ተከታትለው እውነቱን ከውሸቱ መለየትና ለዛሬውም ሆነ ለወደፊቱ አስፈላጊውን መድኃኒት ማግኘት የርስዎ ፋንታ ስለሆነ፤ እኔ ምንም ዓይነት አስተያየት አልሰጥዎትም። ..... » አሉት። ደልቢ በመገረም መልክ፤ አስተያየትህን ከመስጠት ለምን ትቆጠባለህ ? ብሎ ጠየቃቸው። ለአቶ መኮንን መልሱ ቀላል ነበር። « .... ለርስዎ የተጨነቀና ያሰበ አንድ የሥራ ጓደኛችን ጽፎ በወግ አቅርቦልዎታል። የጉዳዩ ወንጀለኛ እኔ ነኝ። ስለዚህ፤ እርስዎ በዳኝነት ወንበር ላይ ተቀምጠው፤ እኔን ወንጀለኛውንና ከሳሹን ፊት ለፊት አጋጥመው ማነጋገር ነው እንጂ የእኔን ሐሳብ በተለይ መጠየቅ ተገቢ የሆነ የአስተዳደር ሥርዓት አይደለም። በዚህ ጉዳይ ከርስዎ የሚጠበቀው ሁለት ነገር ነው። በደረስዎ መረጃ የሚያምኑበት ከሆነ፤ እራስዎን ለመጠበቅ በእኔ ላይ አስፈላጊውን እርምጃ መውሰድ ይኖርብዎታል። አላምንም ካሉ ደግሞ ቀጣፊና አታላይ በሆነው ሰው ላይ ተገቢውን ቅጣት መስጠት ግዴታዎ ይሆናል። ..... » ብለውት ከቢሮው ወጡ።

## የአገር ግዛት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ

የቀድሞው የአዲስ አበባ ፍልውሃ መጠመቂያ ገንዘብ ተቀባይ መኮንን ሀብተወልድ፤ በሳጋር ጉምሩክና በዋናው መሥሪያ ቤት ተዘዋውረው ለስድስት ዓመታት ያህል ከሠሩ በኋላ፤ ከራስ ተፈሪ መኮንን የኢትዮጵያ ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ ጋር በተዋወቁ በሁለተኛው ሳምንት፤ ባልታሰበና ባልተጠበቀ ሁኔታ በአንድ ጊዜ የአገር ግዛት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊነትን በመሾማቸው፤ ያልደነገጠና ያልተገረመ አልነበረም። በንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ውስጥ የሚኒስቴር ዋና ጸሐፊነት የሥራ መደብ ምንም እንኳ ቀደም ሲል እንደ ውጭ ጉዳይና እንደ ጽሕፈት በመሳሰሉት ሚኒስቴሮች የተቋቋመ ቢሆንም፤ በ1913 ዓ.ም ለአገር ግዛት ሚኒስቴር የመጀመሪያው ዋና ጸሐፊ ሆነው የተሾሙት አቶ መኮንን ሀብተወልድ ናቸው።

በዚያን ዘመን የአገር ግዛት ሚኒስትር የነበሩት ሊቀመኳስ ከተማ፤ መኮንን ሀብተወልድን ለመጀመሪያ ጊዜ ሲያይዋቸው፤ ከሲታና ፊተ ኮስታራ በመሆናቸው ሕመምተኛ ናቸው በማለት ተሿሚውን ላለመቀበል፤ ወደ አልጋወራሽ ዘንድ ሄደው፤ « .... ምነው ? ምን በድየዎታለሁ? ይህን ለሞት አንድ ሐሙስ የቀረውን በሽተኛ ይሾሙብኛል ? ..... » ብለው ጠየቁ። አልጋወራሽ ተፈሪም፤ « .... የሰውን ሕይወት በአንድ ሐሙስና በአንድ ዓርብ እያሉ መወሰን በእግዚአብሔር ሥራ መግባት ነው፡ ይህን ሰው ለአገር ግዛት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊነት የሾምነው ፊቱን ሰውነቱን አይተን አይደለም። የጉምሩክን ዋና መሥሪያ ቤት ስንጎበኝ፤ በሒሳብ ሹምነቱ ያሳየውን የሥራ ጥራትና ትጋት በማየታችን፤ ቀጥሎም እንደ ፊተና

አድርገን ለጠየቅነው ሁሉ በሰጠን መልስ ችሎታውን በመመልከታችን፣ ለዚህ ሥራ ተገቢ ሆኖ ስለአገኘነው ነው። እርስዎም በመጀመሪያ በሥራው ላይ ጠንካራነቱንና ደካማነቱን ሳያመዛዝኑ፤ እንዲሁ ክሳቱንና ከስታራነቱን አይተው ፍርድ መስጠት ተገቢ ስላልሆነ፤ ለስድስት ወራት ይሞክሩትና ውጤቱን ይንገሩኝ። .... » ብለው መለሷቸው። በዚህ በአልጋወራሹ ውሳኔ የአገር ግዛት ሚኒስትሩ አልተደሰቱም። ሊቀ መኳስ ከተማ የቀድሞ የምኒልክ ሚኒስትር፣ በተፈጥሮ ጠባያቸው የሚያስቡትንና የሚታያቸውን ሁሉ በግልጽ የሚናገሩ፣ ኃይለኛና ደፋር ሰው ናቸው እየተባለ ቢነገርላቸውም፤ በዚያን ጊዜ ራስ ተፈሪ በኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት እንደራሴነታቸው ሥልጣናቸውን ቀስ በቀስ ያጠናከሩበት ዘመን ስለሆነ፤ በትዕዛዙ መሠረት መኰንን ሀብተወልድን ተቀብለው የሚኒስቴሩን ማሕተም ከማስረከብ በስተቀር እምቢታቸውን መቀጠል አልቻሉም።

የመጀመሪያው የአገር ግዛት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ ሆነው የተሾሙት መኰንን ሀብተወልድ፤ በጥንታዊው የቤተመንግሥት ሥርዓት መሠረት ነጭ የሐር ቀሚስ አጥልቀው ሥራቸውን ከጀመሩ በኋላ፤ ገና ሲያይዋቸው የጠሏቸው አለቃቸው መልካም አስተያየት እንዲያሳድሩባቸው ለመለወጥ ጊዜ አልፈጀም።

ዳግማዊ ምኒልክ በ1901 ዓ.ም ለመጀመሪያ ጊዜ በታሪክ የካቢኔ ሚኒስትሮች ሲያቋቁሙ፤ ለአገር ግዛት ሚኒስትሩ የሰጡት ተግባርና ሥልጣን፤

1ኛ/ ንጉሠ ነገሥቱ ለየአገረ ገዥዎቹ የሚሰጠውን ትዕዛዝ እየተቀበለ የሚያስተላልፍ፣

2ኛ/ አገረ ገዥዎቹን እያስተባበረ፣ በእያንዳንዱ አውራጃና ወረዳ በሕይወት ያለውን የሕዝብ ብዛት፣ እንዲሁም በየጊዜው አዲስ የተወለዱትንና የሚሞቱትን እያስቆጠረ የሚመዘግብ፣

3ኛ/ በእያንዳንዱ አውራጃና ወረዳ ያለውን የእርሻ መሬት ስፋት፣ ለሙንና ጠፉን እየለየ የሚለካና የሚመዘግብ፤

4ኛ/ በእያንዳንዱ አውራጃና ወረዳ ያለውን የሕዝብ ሕይወትና ደህንነት የሚጠብቅ፣

ነው ይላል።

ይህ ከዚህ በላይ የተዘረዘረው የአገር ግዛት ሚኒስትር ሥልጣን በአዲሱ ዋና ጸሐፊ አስተያየት በቂ ሆኖ ስላልተገኘ፤ ሚኒስትሩ በየአገረገዥዎቹ ላይ ስለ አገር አስተዳደር ጉዳይ የሚኖራቸውን ኃላፊነትና ተደማጭነት ከፍ የሚያደርግ አዲስ ፕላን መኰንን ሀብተወልድ አዘጋጅተው አቀረቡ። ይኸውም፡-

1ኛ/ በንጉሠ ነገሥቱ የሚሾሙት አገረ-ገዥዎች ሁሉ፤ በሕዝብ አስተዳደር ጉዳይ መጀመሪያ ተጠሪነታቸው ለአገር ግዛት ሚኒስትሩ መሆን አለበት።

2ኛ/ እያንዳንዱ አገረ ገዥ በንጉሠ ነገሥቱ መልካም ፈቃድ ከተሾመ በኋላ፤ ሕዝቡን የሚያስተዳድርበትን ደንብና ሥርዓት የሚቀበለው ከአገር ግዛት ሚኒስትሩ ሲሆን፤ በተሰጠው መምሪያ መሠረት

በግዛቱ ውስጥ የተፈጸመውንና የደረሰውን ሁኔታ ሁሉ በየወሩ ራፖሩን የሚያቀርበው ለአገር ግዛት ሚኒስትሩ መሆን አለበት።

3ኛ/ የአገር ግዛት ሚኒስትሩም ከየገዥዎቹ በየወሩ የሚደርሱትን ራፖሮች በዝርዝር እያጠና፣ ፍሬ ነገሩን በዓቃቤ ሰዓት ለንጉሠ ነገሥቱ በማቅረብ ካስወሰነ በኋላ፣ አስፈላጊውን መምሪያ ለየገዥዎቹ ይልክላቸዋል።

4ኛ/ እያንዳንዱ አገረገዥ በተሾመበት ግዛት የሕዝቡን ፀጥታና ደህንነት የመጠበቅ ኃላፊነት አለበት። ይኸውም ወንበዴዎችንና ቀማኞችን ለማጥፋት ብቻ ሳይሆን፣ በመንግሥት ላይ ለማመፅ ሤራ የሚያዘጋጁትንና ፀጥታን ለማደፍረስ የሚጥሩትን ወንጀለኞች ሁሉ እየተከታተለ መያዝና ለፍርድ ማቅረብ ሲሆን፣ የዚህንም ሁኔታ በየዕለቱ በምሥጢር ኮድ ለአገር ግዛት ሚኒስትሩ ማስታወቅ አለበት።

5ኛ/ እያንዳንዱ አገረ ገዥ በሚያስተዳድረው ግዛት፣ የጊዜውን የእርሻ ምርትና የከብት እርባታውን በቅርብ መከታተል ቅድሚያ ተግባሩ ሲሆን፣ በድንገት ድርቅ ደርሶ በሕዝቡ ላይ ረኃብ የሚያስከትል መስሎ ሲታየው አደጋው ተስፋፍቶ ከቁጥጥር ውጭ ከመሆኑ በፊት ሁኔታውን በየዕለቱ ለአገር ግዛት ሚኒስትሩ በአስቸኳይ ማስታወቅ አለበት።

የአገር ግዛት ሚኒስትሩም ከአገረ ገዥው በደረሰው ራፖር መሠረት፣ ጉዳዩን ለንጉሠ ነገሥቱ እያቀረበ በማስፈቀድ፣ የዘመኑ የሰብል ምርታቸውና ከምችታቸው ማለፊያ ከሆነበት ከአካባቢው አገሮች፣ በተፋጠነ መንገድ እህል እየተጫነ ለተጐዳው ሕዝብ እርዳታው እንዲደርስ እርምጃ ይወስዳል።

6ኛ/ በመላ ኢትዮጵያ ባሉት አውራጃዎችና ወረዳዎች የተሾሙት አገረ ገዥዎች ቢቻል በየዓመቱ፣ ባይሆን ደግሞ በሁለት ዓመት አንድ ጊዜ አዲስ አበባ እየመጡ፣ በአገር ግዛት ሚኒስትሩ ሰብሳቢነት በየግዛታቸው ስለሚከናወነው ጠቅላላ የሕዝብ አስተዳደር ሁኔታና ስለ ፀጥታ አጠባበቅ ጉዳይ፣ የአንድ ወር ወይም ቢያንስ የሁለት ሳምንት ጊዜ የጥናትና የውይይት ፕሮግራም ሊዘጋጅላቸው ይገባል። በዚህም የውይይትና የጥናት ፕሮግራም፣ አገረ ገዥዎቹ ለሚጠብቃቸው ኃላፊነትና የተግባር አፈጻጸም የሚረዳቸው ጠቃሚ ነገሮችን ለማግኘት ከመቻላቸውም በላይ፣ ከልዩ ልዩ የንጉሠ ነገሥቱ ሚኒስትሮች ጋር ቀጥታ በመነጋገር፣ መንግሥት ያሰበውን ዕቅድና የአገረ ገዥዎቹን ትብብር የሚጠይቀውን የልማት ፕሮግራም በይበልጥ ለማወቅ ያስችላቸዋል።

ሊቀ መኳስ ከተማ የመጀመሪያው የምኒልክ ካቢኔ አባል፣ ይህንን የአገር ግዛት ሚኒስትሩን ሥልጣን እጅግ ከፍ የሚያደርግ ፕላን ነድፈው መኰንን ሀብተወልድ ሲያቀርቡላቸው፣ ከመጠን በላይ ደስታ ተሰማቸው። ወዲያውም ወደ ልዑል አልጋወራሽ ተፈሪ ዘንድ ሄደው፣ መርጠው የሾሙላቸው ዋና ጸሐፊ ምን ያህል አስተዋይና ዐዋቂ መሆናቸውን ከከፍተኛ የአድናቆት ስሜት ጋር በመግለጽ፣

በጥልቀት አጥንተው ያቀረቡትን ፕላን የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ እንዲያጸድቁላቸው ልመና አቀረቡ።

በመሠረቱ ይህን የመሳሰለውን የማዕከላዊውን መንግሥት ሥልጣን የሚያጠናክር ፕላን፣ ተፈሪ መኰንን ከልባቸው የሚፈልጉትና አጥብቀው የሚደግፉት ስለሆነ፣ በሐሳቡ ተስማምተው ወዲያውኑ ጸድቆ በጽሕፈት ሚኒስቴር ማዘዣ እንዲተላለፍ ሙሉ ፈቃዳቸው ሆነ። መኰንን ሀብተወልድም ከአልጋወራሹ ዘንድ ተጠርተው ላደረጉት ጥናትና ላሳዩት ትጋት የማበረታቻ ምስጋና ተሰጣቸው።

የመኰንን ሀብተወልድ ፕላን በተግባር እንዲውል ጉዳዩ ለሚመለከታቸው ሁሉ የጽሕፈት ሚኒስቴር ማዘዣ ሲደርሳቸው፣ ከዋና ዋና ገዥዎቹ መካከል ታላላቆቹ መኳንንቶች፣ አፄ ምኒልክ በአዋጅ ያቋቋሙትን የሚኒስትሮች ሥልጣን ማሻሻል ካስፈለገ፣ ለሁሉም ሚኒስትሮች ይደረጋል እንጂ፣ እንዴት የአገር ግዛት ሚኒስትሩ ለብቻው ተነጥሎ የሥልጣን ማሻሻያ ደንብ ይወጣለታል ? ..... በማለት ተቃውሞአቸውን አሰሙ። አልጋወራሽ ተፈሪም፣ ወደፊት የሌሎቹም ሚኒስትሮች ሥራና ሥልጣን እየተጠና እንደሚሻሻል ካስታወቁ በኋላ፣ አሁን በመጀመሪያ ደረጃ ለአገር ግዛት ሚኒስትሩ የተወሰነው በተግባር መዋል አለበት ብለው፣ የቀረበላቸውን አቤቱታ ሳይቀበሉት ቀሩ።

መኰንን ሀብተወልድ ይህን ፕላን አጥንተው በማቅረባቸው የአለቃቸውን የሚኒስትሩን ከፍተኛ አድናቆትና እምነት ከማግኘታቸውም በላይ፣ ለአፈጻጸሙም ሙሉ ሥልጣን ስለተሰጣቸው በጥቂት ጊዜ ውስጥ እጅግ ታዋቂ ሰው ሆኑ። ነገር ግን፣ የአገር ግዛት ሚኒስቴር የበላይነት ሥልጣን ጉልቶ እንዲታይ በማድረጋቸው፣ አገረገዥዎቹ በጥላቻ ብቻ ሳይሆን እንደ ክፉ ጠላት አድርገው ተመለከቷቸው። በተለይ አልጋወራሹ ከሚያዝያ 1916 ዓ.ም ጀምሮ ለአራት ወራት የልዩ ልዩ አውሮፓን አገሮች ጉብኝተው እስከተመለሱበት ጊዜ ድረስ፣ ታቦትና ንጉሥ እውጭ እድሮ ምን እንቅልፍ ይተኛል ? በሚል አስተሳሰብ፣ መኰንን ሀብተወልድ በአገር ግዛት ዋና ጸሐፊነታቸው በየዕለቱ ከእኩለ ሌሊት ጀምሮ እስከ ንጋቱ ዐሥራ ሁለት ሰዓት ድረስ፣ ከእያንዳንዱ የአውራጃ ገዥ ጋር ስለ ፀጥታው አጠባበቅ በስልክ ሲነጋገሩና ሲጨቃጨቁ ይነጋላቸው ነበር። ከእያንዳንዱ አውራጃና ወረዳ የሰበሰቧቸውን መረጃዎች ጠዋት ሲነጋ የራስ ተፈሪ ተጠባባቂ ባለሥልጣን ለሆኑት ለጦር ሚኒስትሩ ለፊታውራሪ ሀብተጊዮርጊስ ያቀርባሉ። ቀጥሎም በጦር ሚኒስትሩ አማካይነት አገር ሰላምና ጤና መሆኑን ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ እንዲያውቁት ያደርጋሉ።

አንድ ቀን አባ መቻል ሀብተጊዮርጊስ ስለ ፀጥታ ጉዳይ መኰንን ሀብተወልድን ጠርተው ካነጋገሩ በኋላ፣ « .... በአሠራርህና በንቃትህ የአገር ግዛት ሚኒስቴርን እጅግ አስከበርከው አይደለም ወይ ? .... » ይሏቸዋል። መኰንን ሲመልሱ፣ « .... ይህን የገመቱት ታላቁ አስተዋዩ ጌታዬ እርስዎ ነዎት። አገረገዥዎቹ ግን " ይኸ ሲባጐ " በሚል የቅጽል ስም ያፌዙብኛል .... » ይላሉ። አባ መቻል ከፍ ባለ ፈገግታ ፣ « ይኸማ መልካም ነው። ሲባጐ መባል የጥንካሬህ መግለጫ ስለሆነ አትጥላው ! ታውቅ የለም ? እኔን " አንካሳ " እያሉ እንደሚያሙኝ ? .... ታዲያ ከአንካሳ ሲባጐ አይሻልም ? ..... » አሏቸው ይባላል።

መኰንን ሀብተወልድ የአገር ግዛት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ ከሆኑበት ጊዜ ጀምሮ አገረ ገዥዎች ያሳደሩባቸው ጥላቻ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየባሰ ሄደ እንጂ አንዳች

የመሻሻል ምልክት አልታየም። ዋናው ጸሐፊ ከአገረ ገዥዎችና ከመኳንንት ጋር ያላቸውን የሥራ ግንኙነት ለማሻሻል የሚችሉት፣ ለአገር ግዛት ሚኒስቴር የተሰጠውን ደንብ እያጠበቁ መቆጣጠሩንና መጨቃጨቁን ቢያለሰልሱት ነበር። አቶ መኰንን በዚህ ረገድ የሚበገሩ አልሆኑም። ከዚህም የተነሣ፣ ስማቸው እነማን መሆናቸው ባይገለጽም፣ አንዳንዶቹ የአውራጃ ገዥዎች በስውር የላኩባቸውን ማስጠንቀቂያና ዛቻ ችላ በማለታቸው፣ አንድ ቀን ከቢሮአቸው አምሽተው ሲወጡ፣ ሕይወታቸውን ለማጥፋት ያልታወቁ ሰዎች በድንገት ተኩሰውባቸው፣ ተከታያቸው የፀጥታ ጠባቂ ወታደር በጽኑ ሲቆስል፣ እሳቸው በተአምር ድነዋል። ይህም የተሞከረባቸው አደጋ እንዴት እንደነበረና፣ እሳቸውም በምን አኳኋን ለመዳን እንደቻሉ፣ በዝርዝር ታሪኩ አልተገለጸም። በዚያን ጊዜ አብረዋቸው የሚኖሩት እንደልጆቻቸው የሚያሳድጓቸውና የሚያስተምሯቸው ሦስቱ ወንድሞቻቸው (መክብብ፣ አካለወርቅ፣ አክሊሉ) እንዲሁ በደፈናው ከብርቱ አደጋ መዳናቸውን እንጂ ዝርዝሩን ታሪክ አላወቁትም። ከዚህ አደጋ በኋላ፣ ልውል አልጋወራሽ ተፈሪ፣ አገረ ገዥዎቹ በመኰንን ሀብተወልድ ላይ በክፉ መነሣታቸውን ስለተገነዘቡ፣ የዚህን ሰው ሕይወት ማዳን ያስፈልጋል በማለት፣ ከአገር ግዛት ዋና ጸሐፊነት አንሥተው፣ ደረጃ በመጨመር፣ በጥር ወር 1917 ዓ.ም የርሻና የመሥሪያ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር አድርገው ሾሟቸው።

## ወደ እርሻ ሚኒስቴር ቢዛወሩም፣ ለገዥዎች ጤና የሚሰጡ አልሆኑም።

ንጉሠ ነገሥት ዳግማዊ ምኒልክ፣ በ1901 ዓ.ም ለርሻና የመሥሪያ ሚኒስቴር በአዋጅ የሰጡት የኃላፊነት ደንብ፣ በኢያሱም ሆነ በዘውዲቱ ዘመን ሳይነካ በመቆየቱ፣ ለመኰንን ሀብተወልድ ትልቅ ደስታ የሚሰጥ ሆነ። ይኸውም፣ ምኒልክ ባወጡት ደንብ ላይ የተገለጹት ዋና ዋና መመሪያዎች፣ የእርሻ ሚኒስቴር በየአገረ ገዥዎች ላይ ያለው የመቆጣጠር ሥልጣን ከፍተኛ መሆኑን የሚያመለክቱ ስለሆኑ ነው። በደንቡ ውስጥ ከተጠቀሱት ዋና ዋና ጉዳዮች መካከል፡-

1ኛ/ መሬት በደህና እንዲታረስና ብዙ የእህል ምርት እንዲገኝ፣

2ኛ/ ብዙ ከብቶች እንዲረቡና ጤናቸው በከብት ሐኪሞች እንዲጠበቅ፣

3ኛ/ ዛፎች ያለአግባብ እንዳይቆረጡና የአገር ጫካ እንዲጠበቅ፣

4ኛ/ በመኳንንት ግዛት ውስጥ ስንት የለማና ያልታረሰ መሬት እንዳለ ለማወቅ፣ ወይም በጠቅላላው የለማውንና ያልለማውን እየለየ ለመቆጣጠር፣

5ኛ/ አገር ሀብታም እንዲሆን፣ ብዙ ከብቶች ያረቡትንና ብዙ አርሰው ብዙ ምርት የሰበሰቡትን ገበሬዎች፣ እንዲሁም ብዙ ዛፎች ተክለው ውጤቱ ያማረላቸውን ሰዎች በክብር ለመሸለም፣

6ኛ/ በእርሻ ምርት ሆነ በከብት ርቢ፣ ግዛታቸውን በሚገባ ተግተው ሳያሠሩ የቀሩትን እየተቆጣጠረ ለማስቀጣት፣ **ኃላፊነቱ የእርሻ ሚኒስቴር** ነው ይላል።

አዲስ የተሾሙት ዋና ዲሬክተር፣ ይህንን አፄ ምኒልክ ያወጡትን ደንብ ሲመለከቱ፣ ለእርሻ ሚኒስቴር ከዚህ የበለጠ ሥልጣን አያስፈልገውም በማለት እጅግ ፈነደቁ። ከዚህ ቀደም መኰንን ሀብተወልድ ከአገረ ገዥዎች ጋር ከፍተኛ ጠብ ላይ የደረሱት፣ አዲስ ደንብ በማውጣት የአገር ግዛት ሚኒስቴርን ሥልጣን አስፋፍተዋል በመባል እንደሆነ ይታወሳል። አሁን ግን አፄ ምኒልክ ለእርሻ ሚኒስቴር የሰጡት ኃላፊነትና ሥልጣን አንዳች መሻሻል ሳይደረግለት፣ በቀጥታ በተግባር ቢፈጸም፣ አገረ ገዥዎቹ ለመቃወም ምንም ዓይነት መንገድ አይኖራቸውም የሚል ዕምነት አደረባቸው። ወዲያውም ወደ አለቃቸው ወደ ሚኒስትሩ አዛዥ ደገፌ ዘንድ ሄደው፣ « **እኔ በተሰጠኝ የዋና ዲሬክተርነት ተግባር መሥራት የምፈልገው በ1901 ዓ.ም ንጉሠ ነገሥት ምኒልክ ለእርሻ ሚኒስቴር በሰጡት ሥልጣን መሠረት ስለሆነ፣ የክቡርነትዎን ፈቃድ እጠይቃለሁ** » አሉ። የእርሻ ሚኒስትሩ ምንም እንኳ፣ የመኰንን ሀብተወልድ አቀራረብም ሆነ የሐሳብ አገላለጽ የጠነከረ ሆኖ ባይጥማቸውም፣ ጥያቄውን አልተቃወሙም። ይሁን እንጂ ሐሳቡን ሲቀበሉ « **.... የምትሠራው ሁሉ በተለይ ከአገረ ገዥዎች ጋር የሚግባባ እንዲሆን ድከምበት ....** » የሚል ቃል በመወርወር ነክተዋቸዋል።

መኰንን ሀብተወልድ፣ የአለቃቸውን አረንጓዴ መብራት ካገኙ በኋላ፣ ወደ ልዑል አልጋወራሽ ዘንድ ሄደው፣ የተሰጣቸውን ኃላፊነት ከዚህ ቀደም በነበረው ደንብ መሠረት በተግባር ለማሳየት ዝግጁ መሆናቸውንና ስለ አሠራሩም የእርሻ ሚኒስትሩ መስማማታቸውን ገለጹ። ራስ ተፈሪም ይህን ሐሳብ ካደመጡ በኋላ፣ የሰጧቸው ጥልቀት ያለው ከፍተኛ ምክር፣ መኰንን ሀብተወልድ እስከ ሕይወታቸው ፍጻሜ ድረስ ሲያስታውሱት የኖረ ሆነ።

« .... እኛ አንተን ያቀረብንህና ለኃላፊነት ደረጃ ያበቃንህ፣ እኛው ራሳችን የሥራ ችሎታህንና ጥንካሬህን መዝነን ነው። ይኸው አስተያየታችን አሁንም አልተለወጠም። የአገር ግዛት ሚኒስቴርን ዋና ጸሐፊነት ሥራ ለመጀመሪያ ጊዜ የሰጠነው ለአንተ ነው። በዚህም ሥራ አጀማመርህና አያያዝህ የሚደነቅ ሆኖ ነበር። ነገር ግን በአፈጻጸም ላይ ትዕግሥትና ዘዴን ሳታክልበት ቀርተሃል። አገረ ገዥዎቹ መጀመሪያ የዋና ጸሐፊነት ሥራ ምን መሆኑን የሰሙት በአንተ ሹመት ነው። ሁለተኛ ባላሰቡት መንገድ አንተ ባዘጋጀኸው ደንብ የአገር ግዛት ሚኒስትሩ ተቆጣጣሪያቸውና አለቃቸው መሆኑን ሲያውቁ፣ ይኸ ነገር የተፀነሰው በአንተ ነው ብለው አቂሙብህ። ከዚያም አልፈው እንደ ጠላት ተመለከቱህ። በተለይ እነዚህ አፄ ምኒልክ አሳድገው ሕዝብ እንዲያስተዳድሩ ግዛት የሰጧቸው መኳንንቶች እንኳን ለአንተ ለኛም ምቹ አይደሉም። ስለዚህ ከእነሱ ጋር በሰላም እየሠሩ ለመኖር ዘዴና ትዕግሥት ያስፈልጋል .... ። አሁን ደግሞ ለእርሻ ሚኒስቴር በሰጠንህ ኃላፊነት፣ አገረ ገዥዎቹን በሚመለከት ነገር፣ በአፄ ምኒልክ ዘመን የወጣውን ደንብ ተከትዬ ልሥራ ብለሃል። ሐሳቡ ማለፊያ ነው። ደንቡን ተከትሎ መሥራት ኃጢአት የለውም። ነገር ግን ችግሩ ሊፈጠር የሚችለው፣ በአሠራሩ ዘዴና በአፈጻጸሙ ላይ ነው። አገር ግዛት ሚኒስቴር በነበርክ ጊዜ ጠቡን ያጋነነው፣ በአዲሱ ደንብ መሠረት ለየአገረ ገዥዎቹ የተላለፉት ትዕዛዞች ሁሉ የተፈረሙት በአንተ በመሆኑ ነው። ይኸ ትናንት የጉምሩክ ሒሳብ ሠራተኛ የነበረ አልባሌ፣ ከየት መጥቶ ነው ይህን



አቶ መኰንን ሀብተወልድ የእርሻና የሥራ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር፤

ሁሉ ትዕዛዝ የሚያጕርፍብን ብለው ተቆጡ። ነገሩን እነሱ ቦታ ሆነህ ብታስተውለው፣ ምን ያስቆጣቸዋል ? ማለት አትችልም። አንድ ሰው በሥራው ታዋቂ ሆኖ ሊከበርና ሊደመጥ የሚችለው፣ በአንድ ልዩ ተአምር ካልሆነ በስተቀር በሁለትና በሦስት ዓመት አገልግሎት አይደለም። በቂ ጊዜ ይጠይቃል። ስለዚህ፣ ባለፈው ጊዜ የደረሰው ትምህርት ስለሚሆንህ፣ ከአገረ ገዥዎቹ ጋር የሚያግባባህንና ሥራህን ወደ ፍሬ የሚመራውን መንገድ ፈልገህ ማግኘት ይኖርብሀል። .... እንግዲህ ! አሁን በእርሻ ሚኒስቴር በሰጠንህ ኃላፊነት ደንቡን ተከትለህ እንድትሠራ ሲፈቀድልህ፣ ወደ አገረ ገዥዎቹ የሚተላለፈው ማናቸውም ጉዳይ የሚፈረመው በሚኒስትሩ መሆን እንደሚገባው መዘንጋት የለብህም። አንተ እያዘጋጀህ አለቃህ ፈርመውበት ከተላለፈ፣ የአፄ ምኒልክ አገረ ገዥዎች ጉዳያቸው ከአፄ ምኒልክ ሚኒስትር ጋር ስለሚሆን አንተን ነፃ ያደርግሀል። .... በእኛ በኩል ትጋትህ እንደዚሁ ከቀጠለ፣ ታማኝነትህም እንደዚሁ ከዘለቀ፣ ድጋፋችንም ሆነ እርዳታችን ምንጊዜም አይለይህም። ..... ›› ብለው፣ የወደፊቷ ኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ለአዲሱ የእርሻ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ቅንና እውነተኛ የሆነ ምክራቸውን ለገሡዋቸው።

መኰንን ሀብተወልድ ከአልጋወራሹ ባገኙት ምክር መሠረት ከአፄ ምኒልክ ከተሰጠው ዝርዝር ደንብ ውስጥ በጣም ጠቃሚዎች ናቸው ብለው የሚያስቡትን እየመረጡ፣ በተግባር እንዲውል በሚኒስትሩ ፊርማ ለየገዥዎቹ እንዲደርስ አደረጉ። ከተዘረዘሩት ደንቦች ውስጥ በተለይ ታላላቅ መኳንንት ናቸው የሚባሉትን ገዥዎች ያስቆጣቸውና ያበሳጫቸው፣ « .... የእርሻ ሚኒስቴር በየዓመቱ እህል በሰፊው ያመረቱትንና የከብት እርባታውን በደህና ሁኔታ ያስፋፉትን ግዛቶች እየመረጠ የክብር ሽልማት ሲሰጥ፣ በሚገባ ሳይሠሩና ሳያሠሩ የአዝመራውን ወቅት በግዴለሽነት በማሳለፍ ውጤታቸው የተራቆተውን ደግሞ ተከታትሎ በመንግሥት ለማስቀጣት ይችላል። ... ›› የተባለው ሥልጣን ነው።

መኳንንት ገዥዎች ምንም እንኳ ይህን የደረሳቸውን መምሪያ እጅግ አድርገው ቢጠሉትና ከባድ ቅሬታ ቢያድርባቸውም፣ የምኒልክን ሕግ በተግባር አንፈጽምም ለማለት መድፈር አልቻሉም። ሌሎቹ ይህን ያህል የመኳንንትነት መከዳ የሌላቸው ገዥዎች ደግሞ፣ ይህ ደንብ በመካከላቸው ውድድርን የሚፈጥር መሆኑ ባያስደስታቸውም፣ ያለ ልማዳቸው ሳይወዱ በግድ አራሹን ገበሬ በቅርብ ሆነው ለማትጋትና በአዝመራውም ላይ ያለበትን ችግር እያዳመጡ፣ ለእርሻ ሚኒስትሩ ማስታወቅ አስፈላጊነቱ ታያቸው።

በጠቅላላው አብዛኛዎቹ ገዥዎች እየደጋገሙ የሰጡት ትችት « .... ለእርሻ ሚኒስቴር አፄ ምኒልክ የሰጡት ሥልጣን እስከዛሬ ድረስ በተከበረ ማሕደር ውስጥ ተጠብቆ ከሚኖርበት ቦታ ገላልጦ በማውጣት፣ በእኛ ላይ ሳናስበው ከባድ ሥራ ያስጫነብን፣ ያ አገር ግዛት ሆኖ ሲበጠብጠን የቆየ መኰንን የተባለ "ሲባጐ" ነው። .... ›› የሚል ነበር። ይህንን መኰንን ሀብተወልድ በሚገባ ሰምተዋል። ይሁን እንጂ፣ « .... ገዥዎች ሁሉ በእኔ ላይ ምንም ቢማረሩና ከመስመር አልፈው ቢሰድቡኝ፣ በሲባጐ ገመድ በሚገባ ተቋጥሮ ከተላከላቸው መምሪያ መቸውንም ሊያመልጡ አይችሉም ..... ›› በማለት ‹‹ሲባጐ›› የሚል ስም የተሰጣቸው መኰንን አጻፋውን መልሰዋል እየተባለ በአድናቆት ሲነገርላቸው ቆይቷል።

ከየገኸርዎቹ ብዙ ጥላቻና ወቀሳ ቢጉርፍባቸውም፣ መኮንን ሀብተወልድ የእርሻ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሆነው በሠሩባቸው በአራቱ ዓመታት ውስጥ፣ አራሹን ገበሬ ለመርዳት የፈጸሟቸው አንዳንድ ሥራዎች ከመታወቅ አልታገዱም። ከሁሉ ይበልጥ ጉልህ ሆኖ የታየላቸው የሥራ ፍሬ፣ የገበሬዎችን ችግር ለማቃለል፣ የልዩ ልዩ እህል ዘሮችን ከአገር ውስጥና እንዲሁም ከውጭ አገር አሰባስበው፣ በአዲስ አበባ ከተማ በአንድ አማካይ ቦታ ላይ ዘወትር የሚታይ ኤግዚቢሽን ማቋቋማቸው ነው። ገበሬዎቹ ከያሉበት አገር በእርሻ ሚኒስቴር ወጭ ተጋብዘው አዲስ አበባ እየመጡ ኤግዝቢሽኑን ከጉበኙ በኋላ፣ ከቀረቡት ልዩ ልዩ የእህል ዘሮች ውስጥ እየመረጡ ወስደው ለመዝራትና ለመሞከር እንዲችሉ ስለተደረገ፣ ብዙዎቹ አራሾች መልካም ውጤት በማግኘታቸው ደስታቸውን ገልጸዋል። በዚህ ጉዳይ አገረ ገዥዎቹ ምንም እንኳ የመኮንን ሀብተወልድን ሥራ ማድነቅ እጅግ ቢከብዳቸውም፣ በአዲስ አበባ የተደራጀው ቋሚ ኤግዚቢሽን፣ ዕድሜ ለልዑል አልጋወራሽ "ለገበሬዎቹ ጠቃሚ ነው" የሚል አስተያየት ከመስጠት አልተቆጠቡም።

እንደዚሁም፣ በአድዓ ወረዳ በቢሸፍቱ ከተማ አካባቢ መኮንን ሀብተወልድ በመሠረቱት አንድ ትልቅ የእርሻ ድርጅት ውስጥ ስለ ከብት እርባታ ጉዳይ፣ ለገበሬዎች ያቋቋሙላቸው የሥልጠና ፕሮግራም ከፍ ያለ ውጤት መስጠቱ ተመስክሯል። ገበሬዎቹ ከልዩ ልዩ አውራጃ በየተራ እየመጡ፣ ለከብቶቹ የሚያደርጉላቸውን የበሽታ መከላከያና የአመጋገብ ዘዴ እንዲያጠኑ በመደረጉ፣ እርባታውን ለማስፋፋት የረዳቸው መሆኑን ለእርሻ ሚኒስቴር ከምስጋና ጋር የገለጹት ስሜት እጅግ የጋለ ነበር። አንዳንዶቹ ገዥዎችም ለገበሬዎቹ የሚሰጠው ትምህርት ጠቃሚነቱን ስለአመኑበት የሞቀ አስተያየት ለመስጠት ፈቃዳቸው ባይሆንም፣ የተጀመረው እንዲቀጥል ለእርሻ ሚኒስትሩ ማሳሰቢያ ልከዋል።

ከእነዚህ ሌላ ደግሞ፣ በመኮንን ሀብተወልድ አስተሳሰብ፣ የዓሣን ምርት ማስፋፋት ኃላፊነቱ የእርሻ ሚኒስቴር ነው በማለት፣ የወሰዷቸው አንዳንድ እርምጃዎች የሚደነቁ ሆነው ተገኙ። ለምሳሌ፣ ከመተሐራና ከዝዋይ የዓሣዎቹን ዕንቁላሎች እያስመጡ በቢሸፍቱ ሐይቅ በመዝራታቸው፣ በጥቂት ጊዜያት ውስጥ የዓሣው ምርት ተስፋፍቶ፣ በተለይ በጾሙ ወራት ብዙዎቹን ታላላቅ ሰዎች እና በአዲስ አበባ ነዋሪ የሆኑትን የውጭ አገር ዜጎችን ለማርካት ችሏል።

እንግዲህ እንደሚታየው ይህ ሁሉ ጥረት በዘመናዊው አስተያየት የእርምጃ ጉዳና ነው ተብሎ ቢደነቅም፣ መኮንን ሀብተወልድን ከአገረ ገዥዎች ጥላቻ የሚያድን አልሆነም። ያልታደሉት ብቸኛው ታታሪ፣ በመጨረሻው ከአገረ ገዥዎች ጋር ትልቁን ጦርነት የከፈቱት፣ አፄ ምኒልክ ለእርሻ ሚኒስቴር በሰጡት ሥልጣን በአራተኛውና በአምስተኛው አንቀጽ* ላይ « .... **መሬታቸውን በደህና አርሰው ትልቅ ውጤት ያመጡትን ገበሬዎችና ያሠሩትን ሹሞች የእርሻ ሚኒስቴር ክብርና ገንዘብ ይሸልማል። በደህና ሳይሠሩ የቀሩትን ደግሞ ያስቀጣል** ..... » በሚለው ደንብ አፈጻጸም ላይ ነበር። በዚህ ጉዳይ የመኮንን ሀብተወልድ አቋም፣ ሥልጣኑ የተሰጠው ለእርሻ ሚኒስቴር ስለሆነ፣ ደንቡንም የሚያስፈጽመው እርሻ ሚኒስቴር ብቻውን ነው ሲል፣ የአገረ ገዥዎቹ ሐሳብ ደግሞ ይህን ጉዳይ በተግባር ለማዋል እኛም ከእርሻ ሚኒስቴር ጉን ሆነን የውሳኔው ተካፋይ መሆን አለብን የሚል ነበር።

---

* ዝክረ ነገር ገጽ 318 ላይ ተመልከት .... (ማ.ሥ.ወ.መ.)

ነገሩ እየተተራመሰ የአገረ ገዥዎቹ ጉም ጉምታ ማስተጋባት ሲጀምር፣ የእርሻ ሚኒስትሩ ዋና ዲሬክተሩን ጠርተው፣ « .... ይህን አስፈላጊ ያልሆነ ጠብ የጫርከው አንተ ስለሆንክ፣ ሰላም እንዲሰፍን ማድረግ ያንተ ኃላፊነት ነው። እኔ የለሁበትም። ..... » ብለው ቢሮአቸውን ዘጉ። ከዚህ በኋላ አቶ መኰንን እልህ ውስጥ ስለገቡ፣ የሚሠሩት ሁሉ ጠቡን የሚያፋፍም እንጂ፣ የሚያበርድ አልሆነም። በራሳቸው ሥልጣን የእርሻ ኤክስፐርቶች መርጠው የሽልማትና የቅጣት ወሳኝ ኮሚቴ በማቋቋም፣ የእገሌ ግዛት የእርሻ ውጤቱን በማሳመሩ ይህን ያህል የገንዘብ ሽልማት አግኝቷል። የእገሌ ግዛት ደግሞ ምንም ሳይሠራ ወቅቱን በከንቱ በማሳለፉ፣ ይህን ያህል የገንዘብ ቅጣት ተወስኖበታል እያሉ፣ በንቡን በያለበት ማፈንዳት ቀጠሉ። በዚህ ጊዜ አገረ ገዥዎች በሙሉ በተለይም ራስ ደጃዝማቾቹ ተባብረው ለንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱና ለባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴው ለራስ ተፈሪ ባቀረቡት የጠነከረ አቤቱታ፣ « .... እኛ መጀመሪያ ታላቁ ንጉሠ ነገሥታችንን እየተከተልን ለአገር ነፃነት ከጠላት ጋር ስንዋጋ የኖርንና መሥዋዕትነትን የተቀበልን፣ ቀጥሎም በንጉሠ ነገሥታችን ትዕዛዝ አገር በማቅናት ያንን ሁሉ መከራ ያሳለፍን፣ እንዴት በአንድ ሰው ሥልጣን ብቻ የግዛታችን ልማትና ጥፋት እየተመረመረ ይፈረድብናል ? ..... » የሚል ቃል ተጠቀሙ። ንግሥትና አልጋወራሽ በዚህ በደረሳቸው አቤቱታ ብዙዎቹ ራሶችና ደጃዝማቾች እጅግ ማዘናቸውን ከተረዱ በኋላ፣ የሚሻለው መኰንን ሀብተወልድን ከእርሻ ወደ ሌላ ሚኒስቴር ማዛወር ነው ብለው ተስማሙ።

በዚያን ዘመን ተፈሪ መኰንን ምንም እንኳ ለለውጥና ለፈጣን እርምጃ ታጋይ ቢሆኑም፣ ከዚህም በላይ በአልጋወራሽነታቸው ዘውድ ጭነው ንጉሥ በመባል ተጨማሪ ሥልጣን ቢኖራቸውም፣ የመኳንንቶቹን ቅያሜ በቸልታ ለማሳለፍ ባለመቻላቸው፣ ዋና አገልጋያቸውን ነሐሴ 21 ቀን 1921 ዓ.ም ከእርሻ ሚኒስቴር አንሥተው የገንዘብ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር አደረጓቸው። ይህን እርምጃ በመውሰዳቸው፣ አልጋወራሽ ተፈሪ ከአገረ ገዥዎችና ከራስ ደጃዝማቾች ጋር የገጠማቸው ችግር ተወገደ ብለው ተስፋ ሲያደርጉ፣ መኳንንትም በበኩላቸው ያ "ሲባጐ" መኰንን ከእርሻ ሚኒስቴር ተነቀለልን በማለት በጣም ደስ አላቸው።

በዚያን ዘመን አገራችን ላይ በነበረው ፍጹም የሆነ ፊዎዳላዊ ሥርዓት ገባሩን ሕዝብ አስተዳዳሪዎቹ ምን ያህል እንደሚጨክኑበትና እንደሚያስቃዩት ገና በልጅነታቸው የአንድ ክፍለ ሀገር የአሥራት ግብር ጸሐፊ ሆነው የተመለከቱት መኰንን ሀብተወልድ፣ ከእርሻ ወደ ገንዘብ ሚኒስቴር ቢዛወሩም፣ ለገዥዎች ሰላም ለመስጠት የሚተኙ አልነበሩም። በዚያን ዘመን ለእያንዳንዱ ክፍለ ሀገር የሚሾመው አገረ ገዥ፣ ከሕዝቡ ላይ እንዳሰኘው የመሬት ግብርና ታክስ እየሰበሰበ ለመተዳደሪያው የሚያውል፣ የግዛቱንና የጠረፉን ፀጥታ የማስከበር ኃላፊነት አለኝ በማለት፣ የግል ጦሩን እንደተቻለው የሚያስታጥቅ፣ በፍርድም በኩል የራሱን ችሎት እያስቻለ ያለ አንዳች ሕግና ሥርዓት በታየው የሚፈርድ፣ በመሰለው የሚቀጣ ስለሆነ፣ መኰንን ሀብተወልድ ይህን ሁሉ ግፍ በማየት እጅግ ያዘኑና የተበሳጩ ናቸው። እርግጥ ! ይህን የመሰለው የመከራ ቀንበር ከወደቀበት ከአርሶ አዳሪው ሕዝብ ትከሻ ላይ ለማላቀቅ፣ የአልጋወራሽ ተፈሪ ብርቱ ምኞት መሆኑን ስለሚያውቁ ጽኑ ተስፋ ያደርጋሉ። ይሁን እንጂ፣ ይህን ሁሉ የሕዝብ ችግር በአንድ ጊዜ ለመደምሰስ ኃይልና አቅም ስለሌለን፣ ደረጃ በደረጃ እንሥራ የሚለውን የራስ ተፈሪን ዕምነት ለማፋጠን፣ የታዋቂው የራጉኤል ደብተራ የአለቃ ሀብተወልድ ልጅ እየሮጡ ብዙ ጠላት በማፍራታቸው፣ ለአልጋወራሹ የፖለቲካ አመራር ምቹ መሆን አልቻሉም።

---- የአገር ግዛት ዋና ጸሐፊ ከሆኑ በኋላ፤ የየክፍለ ሀገሩ ገዥዎች ሁሉ የሕዝቡን አስተዳደር በሚመለከት ጉዳይ መጀመሪያ ተጠሪነታቸው ለአገር ግዛት ሚኒስትሩ መሆን አለበት ብለው የታገሉት፣

---- የእርሻ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሲሆኑ፤ ገዥዎች በልማት ሥራዎች ላይ በግዴታ ተካፋይ እንዲሆኑና ገበሬዎችም ከመንግሥት ጋር ቀጥታ ግንኙነት እያደረጉ የሚያስፈልጋቸውን እርዳታ እንዲያገኙ ያንን ያህል የተዋጉት፣ የማዕከላዊው የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ሥልጣን እንዲጠነክርና፤ ኢትዮጵያ በአንድ አስተዳደር ውስጥ አንድትጠቃለል ለማድረግ ነበር። ሆኖም፤ መኰንን ሀብተወልድ ከጉምሩክ ሒሳብ ሹምነት ተነሥተው፤ በእነዚህ በሁለት ሚኒስቴሮች ውስጥ ሁለተኛ ሰው በመሆን ብዙ ሥልጣን አግኝተው በሠሩባቸው በስምንቱ ዓመታት ውስጥ፤ ብዙ የሥራ ፍሬዎች ቢያሳዩም በዚያው መጠን ብዙ ጠላቶች አፍርተዋል።

---- ምድረ መኳንንት፤ ዓይናቸውን ማየት አይፈልጉም። እሳቸውም መኳንንትን አይወዱም።

---- አገረ ገዥዎች፤ መጥላት ብቻ ሳይሆን ሊያጠፏቸውም ይፈልጋሉ። እሳቸውም፤ ገዥዎች ሕዝቡን በአስተዳደር የሚበድሉ፣ ፍርድ የሚያዛቡ፣ ለሥልጣኔ እንቅፋቶች ናቸው ብለው ያማርራሉ።

---- ሚኒስትሮች፤ ችኮ የሆነ ሰው ነው እያሉ አያስጠጓቸውም።

---- እሳቸውም፣ ሚኒስትሮቹ ችሎታ የሌላቸው በመሆናቸው አልጋወራሽን አይረዷቸውም እያሉ ይነቅፋሉ።

እንግዲህ ምን ይሻላል ? ..... መኰንን ሀብተወልድ አገር አፍቃሪና ለሕዝብ ተቆርቋሪ መሆናቸውን አልጋወራሽ ተፈሪ ተረድተውላቸዋል። ነገር ግን በየምክንያቱ ከየመኳንንቱ ጋር የሚከፍቱት ጦርነት፤ እንኳንስ ለአገር መሻሻልና ልማት ያላቸውን ዓላማ ከግብ ለማድረስ ይቅርና፤ ለግል ሕይወታቸውም ዋስትና የሚኖራቸው አልሆነም። ስለዚህ፣ ለገንዘብ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተርነት የተሰጣቸውን አዲሱን ኃላፊነት ከመጀመራቸው በፊት፣ መኰንን ሀብተወልድ መመከር አለባቸው ተብሎ፤ ከቅርብ ወዳጆቻቸው መካከል ጥቂቶቹ ተመርጠው ተመደቡላቸው። ለመካሪዎቹ የተሰጣቸው ሚሲዮን፣ መኰንን ሀብተወልድ ከእንግዲህ ወዲህ ከየመኳንንቱ ጋር በሥራ ምክንያት ቀጥታ መጋጨትንና መጋተርን አቁመው፤ የተሰጣቸውን ሥልጣን በለሰለሰ መንገድና በዘዴ እንዲያከናውኑ ነበር። በዚህ ጉዳይ አቶ መኰንን አቋማቸውን ሲገልጹ፤ « .... እኔ በምንም ምክንያት ለመኳንንት ሆነ ለገዥዎች አልሰግድም። እርግጥ ! መንግሥት የሰጣቸውን ሹመትና መብት አከብራለሁ። ነገር ግን ለአገር እርምጃ ይጠቅማል ብዬ የማስበውን እውነቱን ከመናገር ወይም በጽሑፍ ከመግለጽ አልቆጠብም። እኔ ቀርቤ ገዥዎቹን እንዳስተዋልኳቸው፤ እነሱ ድሀን ይንቃሉ። በተጨማሪም ድሀው መታዘዝና መስገድ ግዴታው ነው ብለው ያምናሉ። ከዚህ በላይ ደግሞ ድሀውን እያስጨነቁ እንደፈለጋቸው እያሳረሱ፣ እንዳሻናቸው እያስገበሩ፣ ተንደላቀው የሚኖሩት፤ ወደዚህ ዓለም ሲመጡ አብረውት እንደተወለዱት የተፈጥሮ መብት አድርገው በመቁጠር ነው። ይህንን ግፍ የሚከላከል የምድራዊ ሕግ ለጊዜው ባይኖርም፤ ክርስቲያኖች በመሆናቸው የሰማዩን ሕግ በማሰብ ድሀውን ከማሠቃየት

ማቆም ነበረባቸው። ግን ምን ይሆናል ? .... እነሱ እንደዚህ አያስቡም። አንድ ቀን የዚህን ሕዝብ እንባ ፈጣሪ ሰምቶ ፍርዱን እስከሚሰጥ ድረስ ሁላችንም መታገሥ ቢኖርብንም፣ የእነሱ ተገዢዎች አለመሆናችንን በየአጋጣሚው እንዲገነዘቡት ለማድረግ መድፈር አለብን። ..... »

የተላኩት ሽማግሌ መካሪዎች፣ የመኰንን ሀብተወልድ ንግግር እጅግ ከበዳቸው። ምን ቢደርስበት ይሆን ? በታላላቆቹ ሰዎች ላይ እስከዚህ የተማረረው ? እያሉ ሲጨነቁ፣ ከመካከላቸው አንደኛው በድንገት ተነሥተው፣ « .... ለመሆኑ አንተን እስከዚህ ደፋር ያደረገህ ምንድነው ? .... ለዚህ ደረጃ ያበቁህን አልጋወራሽ ተፈሪን ተማምነህ ነው ? .... ወይስ ሌላ ምክንያት አለህ ? .... » ብለው ጠየቋቸው። መኰንን ሲመልሱ፣ « .... ባታስብበት ነው እንጂ፣ ደሀ ምንጊዜም ደፋር ነው። ከዚህ ከሚሠቃይበት ዓለም ምን ይቀርብኛል ብሎ የሚፈራ ይመስልሃል ? ... በዚህ ዓለም ፍርሃት የሚያስጨንቀው መኳንንትን ነው። ይህን የመሰለ የምቾት ሕይወት፣ ይህን የመሰለ ወርቅ፣ ይህን የመሰለ መከዳ፣ እንዴት ትቼ እሄዳለሁ ? ብሎ የሚሠጋ እሱ ነው። ደሀ ግን ይህ ሁሉ ጭንቅ የለበትም። ..... እኔ ይህን ሁሉ ከልቤ የሚሰማኝን የምነግራችሁ በአልጋወራሽ ላይ ተመርኩዤ አይደለም። እርግጥ በአልጋወራሽ ተፈሪ ላይ አንድ ትልቅ ዕምነት አለኝ። ይኸውም፣ ኢትዮጵያን ከጨለማ ወደ ብርሃን የሚያሻግሯት እሳቸው ብቻ ናቸው ብዬ የማምን ነኝ። በዚህ ምክንያት ከልቤ እወዳቸዋለሁ። በቅን አገለግላቸዋለሁ። እስከ መጨረሻም እሠዋላቸዋለሁ። ከዚህ ሌላ ግን እኔ ከመኳንንት ጥላቻና ዛቻ የምድነው ወይም የምተርፈው በእሳቸው ነው ብዬ ስማቸውን አላስነሣም። እኔ ለሕይወቴ መኖርና አለመኖር የምተማመነው በፈጣሪዬ ብቻ ነው። ... »

ከዚህ በላይ እንደታየው የመኰንን ሀብተወልድ አቋም፣ በጊዜው ከነበረው አስተሳሰብና ሁኔታ ጋር ሲመዘን፣ እንደ ዕብሪተኛና እንደ ማን አለብኝ የሚቆጠር ይሆናል ። ሆኖም "መካሪ" የሆኑት ሽማግሌዎች የአልጋወራሹ አደራ ስለከበዳቸው፣ በአቦ-በሥላሴ ብለው በመለመን፣ መኰንን ሀብተወልድ አዲሱ ሥራቸውን በረጋና በለሰለሰ መንፈስ እንዲጀምሩ አስደረጉ። በዚህ ጉዳይ አንዳንዶቹ ታላላቅ ሰዎች፣ ይኸን መኰንን ሀብተወልድ የተባለ የአንድ ደብተራ ልጅ ይህን ያህል መለማመጥና መታገሥ ለምን አስፈለገ ? እያሉ አልጋወራሹን ሲጠይቁ፣ « .... ሰውየው ሥራ ዐዋቂና በሚያምንበት የሚፀና ጠንካራ ሰው ከመሆኑም በላይ፣ በአገር ወዳድነቱና በታማኝነቱ ብዙ ሊረዳኝ ይችላል ብዬ በማሰብ ነው .... » የሚል መልስ አግኝተዋል። እንደ እውነቱ ከሆነ፣ ይህ አልጋወራሽ ተፈሪ ያደረባቸው አስተያየት ወደፊት ጊዜው ሲደርስ በተግባር ላይ ውሎ የምናየው ይሆናል።

መኰንን ሀብተወልድ በተመከሩት መሠረት፣ በገንዘብ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተርነታቸው ድምፃቸውን አጥፍተው ከማንም ጋር ሳይጋጩ፣ ስለአስተዳደርም ጉዳይ ምንም ዓይነት ጥናት ወይም አስተያየት ሳያቀርቡ ለብዙ ወራት በመቆየታቸው፣ አንድ ቀን አልጋወራሹ ጠርተዋቸው፣ « .... ምነው ወደ ገንዘብ ሚኒስቴር ከሄድክ ብኋላ መኘታ አበዛህ ? .... ያን ሁሉ ንቃት፣ ያን ሁሉ ትጋት የት አደረስከው ? .... » ብለው ጠየቋቸው። መኰንን፣ ለመልሱ ማሰብ አላስፈለጋቸውም። እርሻ ሚኒስቴር ሆኜ የነበረብኝን ከባድ ኃላፊነትና ብርቱ ድካም ተረድተውልኝ፣ ወደ ገንዘብ ሚኒስቴር ካዛወሩኝ ዕለት ጀምሮ ያገኘሁት ሰላምና የተደገፍኩት መከዳ፣ ተኝቶ እንቅልፍ መጥገብን እንጂ ንቃትን አልሰጠኝም አሏቸው። በሌላ አነጋገር መኰንን የገለጹት ስሜት፣ እንቅልፉን ያበዙብኝና ንቃቱን

ያቋረጡብኝ እርስዎ ነዎት ለማለት መሆኑን አልጋወራሽ ስለተረዱላቸው፤ ቆይ ግዴለም ! የምትወደውን እስክ አሽከምህ ድረስ በትዕግሥት ጠብቅ። ብለው የሚፈልጉትን እንደሚያገኙ ተስፋ ሰጧቸው።

ከዚህ በኋላ፤ መኰንን ሀብተወልድ በአዲስ መንፈስ አእምሮአቸውን ማነቃቃት ሲጀምሩ፤ ሳያስቡት በድንገት በመልዕክት ወደ ግብፅ አገር ሄደው በእንግሊዞች ማሕበር ሲካሄድ የነበረውን "አቢሲኒያ" የተባለውን ባንክ በኢትዮጵያ መንግሥት ስም ተደራድረው እንዲገዙ፤ የአልጋ ወራሽ ንጉሥ ተፈሪ ትዕዛዝ ደረሳቸው። መኰንን ሀብተወልድ ምንም እንኳ ስለ ባንኩ ግዥ በተደረገው ጥናት የተካፈሉና ጉዳዩን ደህና አድርገው የሚያውቁት ቢሆኑም፤ ወደ ግብፅ አገር ሄደው ግዥውን የሚፈጽሙት አለቃቸው የገንዘብ ሚኒስትሩ በጅሮንድ ዘለቀ አግደው ናቸው እንጂ እኔ እሆናለሁ ብለው አልጠበቁም ነበር።

" ባንክ ኦፍ አቢሲኒያ " በ1897 ዓ.ም በንጉሠ ነገሥት አፄ ምኒልክ መልካም ፈቃድ በእንግሊዞች ማሕበር ከተቋቋመ በኋላ፤ በመላ ኢትዮጵያ የሞኖፖል ሥልጣን ይዞ ሲሠራ የቆየ ነው። ባንኩ በዚህ አቋሙ ከሐያ ሁለት ዓመታት በላይ አገልግሎት ከሰጠ በኋላ፤ የነበረው ካፒታል ተገዝቶ፤ "የኢትዮጵያ መንግሥት ባንክ " እንዲባል ንጉሥ አልጋወራሽ ተፈሪ ስለፈለጉና እንግሊዞችም ስለተስማሙ፤ የግዥውንና የሥልጣን ዝውውሩን ጉዳይ ተደራድሮ ለመፈራረም፤ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ወደ ካይሮ የተላኩት ከአቶ አየለ ገብሬ (ኋላ ብላታ) ጋር ነበር። የንጉሥ ተፈሪ መልዕክተኞች የባንኩን ግዥ ውል ለመፈጸም በግብፅ አገር በቆዩባቸው በሁለቱ ወራቶች ውስጥ፤ መኰንን ሀብተወልድ ከአገሩ የፊናንስ ሰዎች ጋር ግንኙነት በመፍጠር፤ የግብፅ የገንዘብ ሚኒስቴር የሚካሄደው በምን መልክ እንደሆነና እንዲሁም ስለ መሬት ግብርና ታክስ አሰባሰብ፤ ከዚያም በላይ ለመንግሥት መሥሪያ ቤቶች መተዳደሪያ የሚዘጋጀው የበጀት ድልድል እንዴት እንደሆነና፤ በዚህም ጉዳይ የገንዘብ ሚኒስትሩ ሥልጣን ምን መሆኑን ለማጥናት ጥሩ አጋጣሚ ሆነላቸው። በዚህ አኳኋን የባንክ ኦፍ አቢሲኒያን ግዥ ፈጽመው አዲስ አበባ ከተመለሱ በኋላ፤ የመኰንን ሀብተወልድ የመጀመሪያ እርምጃ የሚከተለውን ሐሳብ ለንጉሥ አልጋወራሽ ተፈሪ ማቅረብ ነበር"።

## አገረ ገዥዎች በበጀት ይተዳደሩ
## <u>ገበሬው ቀጥታ ለመንግሥት ይገብር!</u>

(መ.ሀ.ወ.)

‹‹ .... ባንክ ኦፍ አቢሲኒያን ለመግዛት የንጉሥ አልጋወራሽን መልዕክት ይዤ ግብፅ አገር በቆየሁባቸው ቀናቶች ውስጥ፤ በትርፍ ጊዜዬ አንዳንድ ጠቃሚ መስለው የታዩኝን ጉዳዮች ሳጠና ሰንብቻለሁ። ከነዚህም ውስጥ፤ ዋና ነገር አድርጌ የተመለከትኩት፣ የግብፅን የገንዘብ ሚኒስቴር ሥልጣንና የሥራ አፈጻጸም ነው። ንጉሥ አልጋወራሽ ከማንም የበለጠ እንደሚያውቁት፤ እንደ ኢትዮጵያ ጥንታዊ የታሪክ ሀብት ያላት ግብፅ፤ ምንም እንኳ እስካሁን ድረስ ከእንግሊዞች አስተዳደር ያልተላቀቀች ብትሆንም፤ ከአውሮፓ የሚተላለፈውን ሥልጣኔ በቀላሉ ለመቀበል መንገዱ ላይ በመገኘቷ፤ ከማንም የበለጠ ዕድል ነበራት። ነገር ግን ሕዝቡ የሃይማኖቱ ጉዳይ እጅግ የተጫነው ከመሆኑም በላይ፤ በየሰዓቱ ሻይ እየተጋተ፣ ጫት እያኘከ፣ ለመኘታው ቅድሚያ የሚሰጥ በመሆኑ፤ ከአውሮፓ ተነሥቶ እደጁ ድረስ የሚመጣለትን ሥልጣኔ በሚገባ ተቀብሎ አለመጠቀሙን በቀላሉ መረዳት

ይቻላል። ይህ ሕዝብ ምናልባት ወደፊት ከእንግሊዞች አስተዳደር ወጥቶ ሙሉ ነፃነቱን ሲያገኝ፤ ለሥልጣኔ ዕድገት እጅግ ሊበረታና ሊፈጥን ይችላል እየተባለ ሲነገር ስምቻለሁ። እኔ ግን አልመሰለኝም። ከዚህ ከለመደው የስንፍና ሕይወት ለመላቀቅ ረዥም ጊዜ ሳይወስድበት አይቀርም።

ቀደም ብዬ እንደጠቀስኩት፤ ባሪያም ረጋ ብዬ ያስተዋልኩት፤ ስለ ገንዘብ ሚኒስቴር አቋምና አሠራር ነው። በዚቹ በማውቃት ፈረንሣዊኛ፤ ከዋና ዋና ኃላፊዎቹ ጋር በቀጥታ በመነጋገርና የሚሰጡኝንም ዶክማዎች በማንበብ፤ አንዳንድ ጊዜም የጉዳዩ አገላለጽ ጠንከር ሲልብኝ፤ አሌክሳንድሪያ ከሚማሩት ወንድሞቼ መካከል በአማርኛ ሻል የሚለውን መክብብን ቅዳሜና እሑድ እያስመጣሁ በትርጉም ስለረዳኝ፤ ጠቃሚ መስሎ የታዩኝን ሁሉ በማስታወሻ ይዣቸዋለሁ።

በእኔ በባሪያም አስተያየት፤ ንጉሥ ጌታችን የሚደክሙላትን አገራችን ኢትዮጵያን ለማሻሻል፤ የገንዘብ ሚኒስቴርዎ ድርሻውን ማበርከት የሚችለው፤

1ኛ/ በመላ ኢትዮጵያ ከመሬት ግብር እና ከልዩ ልዩ ታክስ፤ እንዲሁም ከልዩ ልዩ የሚኒስቴር መሥሪያ ቤቶች የሚገኙትን ገቢዎች እየሰበሰበ፤ የመንግሥት ሀብት እንዲሆን የማድረግ ሥልጣን ሲኖረው፤

2ኛ/ በተገኘው ገቢ መሠረት፤ ለመንግሥት ሥራዎች ማካሄጃና ለልማት ማንቀሳቀሻ፤ ለእያንዳንዱ ሚኒስቴርና ክፍለ ሀገር፤ የዓመት በጀት የመደልደልና ወጭውን የመክፈል ኃላፊነት ሲሰጠው ነው።

በዚህ አኳኋን እንዲሠራ ከተደረገ፤ የገንዘብ ሚኒስቴርዎ በአራት የሚከፈሉ የሥራ ዘርፎች ይኖሩታል ማለት ነው። እነዚህም፡-

ሀ/ ጠቅላላ የመንግሥት ገቢዎች መሰብሰቢያ፤
ለ/ የመንግሥት መሥሪያ ቤቶች በጀት መደልደያና ማዘጋጃ፤
ሐ/ የሥራ ማስኬጃዎች ወጭ መክፈያ፤
መ/ የገቢዎችና የወጭዎች መቆጣጠሪያ፤ ናቸው።

በዚህ በቀረበው ሐሳብ ላይ ለንጉሥ ጌታችን አልጋወራሽ ውሳኔ እጅግ ከባድ ሆኖ የሚታየኝ፤ የጠቅላላ ገቢዎችን መሰብሰቢያና የበጀቱን መደልደያ ሥልጣን ለገንዘብ ሚኒስቴር መስጠቱ ነው። በዚህ በኩል ትልቁ ችግር የሚፈጠረውም፤ በበጀት መተዳደርን እንደ ትልቅ ጥቃት አድርገው ከሚቆጥሩት፤ ከየክፍለ ሀገሩ ገዥዎች ጋር እንደሚሆን በግልጽ ይታየኛል። ስለዚህ፤ በእኔ በባሪያም አስተያየት፤ ከሁሉ በፊት መወሰን ያለበት፤ አገረ ገዥዎች በየግዛታችን ጠረፍ ያገር ነፃነት ተከላካዮች ነን ብለው በየግላቸው የሚያቋቁሙትን ጦር አፍርሶ፤ ለመላዋ ኢትዮጵያ በሚያገለግል በአንድ የንጉሡ ነገሥት የጦር ሠራዊት ድረጅት ውስጥ ማጠቃለል ነው። ባለንበት ጊዜ፤ ዕድሜ ለመሪያችን ለንጉሥ አልጋወራሽ ተፈሪ፤ ኢትዮጵያ የዓለም መንግሥታት ማሕበር አባል ሆና የተከበረ ወንበር ስለያዘች፤ እንደ ቀድሞው ዘመን ማንም የውጭ መንግሥት በጥጋብ ተነሥቶ ነፃነቷን ለመድፈር ይቃጣል ተብሎ አይጠበቅም። ሆኖም እንደ ኢትዮጵያ የመሰለው አልሠለጠነም እየተባለ የሚወቀስ አገር፤ በዚህ ማሕበር ላይ ብቻ ተመክቶ መኖር ስለማይቻል፤ የመላዋን ኢትዮጵያን ዳር ድንበር ለመጠበቅ የሚቋቋመው የንጉሡ

ነገሥቱ የጦር ኃይል፤ የሚያስተማምን ድርጅት ያለው መሆን አለበት። ይህ ሐሳብ ጸድቆ በአዋጅ ከተገለጠ በኋላ፤ ቀጥሎ የሚወሰደው ትልቁ እርምጃ፤ ገበሬና ገባር የሆነውን ሕዝብዎን እስከዛሬ ካለበት ሥቃይና መከራ ለማላቀቅ የሚያስችለውን መንገድ ነው። ይኸውም፤ ገበሬው ሕዝብዎ በቀጥታ የሚገብረው ለመንግሥት እንዲሆን በማድረግና፤ መንግሥትም በሚያገኘው ገቢ አገሩን ለማስተዳደር የዓመት በጀት መድቦ ለገዥዎቹና ለሠራተኞቻቸውም የወር ደሞዝ ወስኖ በመስጠት ነው። በተለይም ገበሬው ሕዝብዎ አርሶ ከሚያገኘው ምርት በሕግ የተተመነለትን ግብር በቀጥታ ለመንግሥት ገቢ በማድረግ ከመንግሥት ጋር ቀጥታ ግንኙነት ስለሚኖረው፤ መብቱ በሕግ የሚጠበቅለት፤ እሱም ግዳጁን በሕግ የሚፈጽም ይሆናል። በዚህ ዓይነት አሠራር ሕዝቡ በመንግሥት ላይ ሙሉ ዕምነት ስለሚያድርበት የአገር አንድነትንም በበለጠ ለማጠንከር ሊረዳ ይችላል።

ይህ ውሳኔ በአዋጅ ተገልጦ በሥራ ላይ እንዲውል ከመደረጉ በፊት፤ በየክፍለ ሀገሩ አንዳንድ "የአስረጂ ኮሚሲዮን" ተቋቁሞ፤ በአንድ በኩል እስካሁን ሲሠራበት የኖረው የግብር አከፋፈል ገበሬውን ሕዝብ እጅግ አድርጎ የጐዳ እና መንግሥትን ያልጠቀመ መሆኑን፤ በሌላ በኩል ደግሞ አዲስ የታሰበው አሠራር፤ የአገሩን ልማት ለማስፋፋት የሚያፋጥን እና የገበሬውን ችግር የሚያቃልል፤ መንግሥትንና ሕዝብንም በማናቸውም ጉዳይ የሚያቀራርብና የሚያስተባብር መሆኑን ለሕዝቡ እንዲያስረዳ ማድረግ፤ እጅግ አስፈላጊ መስሎ ታይቶኛል። በእኔ በባሪያዎ ግምት፤ በዚህ በአዲሱ አሠራር አገረ ገዥዎቹ ምንም እንኳ ተቃዋሚነታቸው ባያጠራጥርም፤ የመተዳደሪያ በጀት የሚደለደልላቸው፤ እንደየግዛታቸው ስፋት፤ እንደየነዋሪው ሕዝብ ብዛት፤ እንደየልማቱ ወይም ምርቱ ዕድገት ተጠንቶ መሆኑ ሲነገራቸው፤ እኔ ከሌላው አንሳለሁ፤ ወይም አድሎ ይደረግብኛል የሚል ሥጋት ላያድርባቸው ይችላል። ይሁን እንጂ፤ በዚህ በቀረበው ሐሳብ ላይ አስተያየት ስጡበት ተብለው ከተጠየቁ፤ ግዛታቸውን መንግሥት ለክቶ በሚሰጣቸው በጀት ለማስተዳደር፤ እነሱም በወር በሚቆረጥላቸው ደሞዝ ለመተዳደር አይሆንልንም የሚል ተቃውሞ እንደሚያቀርቡ መጠበቁ አይከፋም። እንደዚህም በማለት ደፍረው ከመጡ፤ መልሱ የሚቸግረን አይደለም። ንጉሠ መሪያችን ኢትዮጵያን የዓለም መንግሥታት ማሕበር አባል ለማስደረግ ፤ አገሬን ወደ ሥልጣኔ ለማሻገር፤ የሰውን ልጅ ሰብዓዊ መብት ለማስከበር፤ አስተዳደሩን ከፊውዳል አመራር ወደ ሕጋዊ ሥርዓት፤ ከገባር ጭቆና ወደ ትክክለኛ ፍርድ እለውጣለሁ ብለው፤ ቃል መግባትዎን አጠንክሮ ማስታወስ ያስፈልጋል። በዚህም መሠረት ፈረንጆቹ የተባለውን ሁሉ እንደሚከታተሉ፤ የተሠራውንና ያልተሠራውን እያመሳከሩ ለዓለም መንግሥታት ማሕበር እንደሚጽፉብን ማስረዳት አለብን። ንጉሠ መሪያችንም አገርዎን ለማሠልጠንና ለማሳደግ ሌት ተቀን መድከምዎን አላቋረጡም። አሁንም ይህን በገባሩ ሕዝብዎ ላይ የኖረውን ችግር ለማቃለል መወሰንዎን ሕዝብዎ እንዲያውቀው ቢደረግ፤ የአገረ ገዥዎቹና እንዲሁም የጥቂቶቹ ባለ ጉልቶች ተቃውሞ፤ ከአፍ ወደ አፍ የሚተላለፍ ወሬ ከመሆኑ በስተቀር፤ ወደ ትልቅ ጉዳይ ተሻግሮ የሚያሳስብ ሊሆን አይችልም።

እንግዲህ! ከ1897 ዓ.ም ጀምሮ በእንግሊዞች ማህበር ተቋቁሞ በአገራችን ላይ ሲነግድ የኖረውን ባንክ አፍ አቢሲኒያን ገዝተው የኢትዮጵያ መንግሥት ሀብት እንዲሆንና የተሟላ አገልግሎት እንዲሰጥ ሲያደርጉ፤ ባንኩም በምስልዎ ገንዘብ እያተመ ለመንግሥትዎ ሥራ ማካሄጃና ለሕዝብዎ መገበያያ እንዲሆን ሥልጣን ሲሰጡት፤ ለአገራችን የሥልጣኔ እርምጃ መንገድ ከፋች ስለሆነ፤ ከዚሁ ጋር ገባር

ሕዝብዎን ከአስገባሪዎች ጭቆና ለማዳን በሚወስዱት እርምጃ፤ መላው የኢትዮጵያ ሕዝብ ከርስዎ ጋር ነው እያልኩ ሐሳቤን እዚህ ላይ አቆማለሁ።

ባሪያዎ መኰንን ሀብተወልድ

መኰንን ሀብተወልድ ይህን ከዚህ በላይ የተገለጸውን ሐሳብ ለንጉሥ አልጋወራሽ ተፈሪ ሲያቀርቡ መጀመሪያ የአለቃቸውን የገንዘብ ሚኒስትሩን ስምምነት በማግኘት ነበር። በዚያን ጊዜ ሚኒስትር የነበሩት በጅሮንድ ዘለቀ አግደው፤ የውጭ አገር ትምህርት የተማሩና የዘመኑን የአውሮፓን ሥልጣኔ የሚከታተሉ በመሆናቸው መኰንን ሀብተወልድ ግብፅ አገር በቆዩበት ጊዜ አጥንተው ያቀረቡት ሐሳብ እንዲጸድቅ ከልባቸው ቢደግፉም፤ ንጉሥ አልጋወራሽ፤ ከሁሉ በፊት ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ፣ ቀጥሎም ታላላቆቹ መሳፍንትና መኳንንት እንዲስማሙበት ለማድረግ ሳይሳካላቸው ቀረ። በተለይም ታላላቅ መኳንንት የሆኑት አገረ ገዥዎች ይህን ሥልጣናቸውን የሚበታትን ፕላን መዘጋጀቱን ሲሰሙ፤ ያልተጠበቀ ችግር ያመጡ ይሆናል የሚል ሥጋት ስለተፈጠረ፤ ንጉሥ አልጋወራሽ ወደፊት ንጉሠ ነገሥት ሆነው የምኒልክን የሥልጣን ዘውድ እስኪጭኑ ድረስ፤ የመኰንን ሀብተወልድ ሐሳብ በምሥጢር ተይዞ ቢቆይ ይሻላል አሉ። ይህም ከተወሰነ በኋላ፤ መኰንን ሀብተወልድ በዚሁ በገንዘብ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተርነት ሥልጣናቸው አገረ ገዥዎችን ከመተንኳኰስ አላርፍ ብለው ማስቸገራቸውን ስለቀጠሉ፤ አልጋወራሽ ተፈሪ የንጉሠ ነገሥትነት የንግሥ በዓላቸውን ከማክበራቸው በፊት መኰንን ሀብተወልድን በያዙት ማዕረግ ወደ ንግድ ሚኒስቴር ማዛወር ግዴታ ሆነባቸው።

አልጋወራሹ ይህን እርምጃ የወሰዱት፤ ታማኝ አገልጋዬ በሚሏቸው ሰው ላይ ያላቸውን ዕምነትና መልካም አስተያየት ለውጠው አይደለም። ዘውዲቱ ምኒልክ ከሞቱ በኋላ፤ የንግሥ በዓላቸውን በጥሩ ዝግጅት ለማክበር በሚደክሙበት ወራት፤ የመኳንንትንና የመሳፍንትን፣ በተለይም የአገረ ገዥዎችን ሙሉ ትብብር ማግኘት እጅግ አስፈላጊያቸው ስለሆነ፤ መኰንን ሀብተወልድ በገንዘብ ሚኒስቴር ሥራ ላይ ሆነው በአንዳንድ ጉዳዮች ላይ የሚጭሩት እሳት ችግር እንዳይፈጥርባቸው በመሥጋት ነበር። በመሠረቱ፤ የአልጋወራሹ ሥጋት ትክክል መሆኑን መገንዘብ የተቻለው፤ የመኰንን ሀብተወልድ ከገንዘብ ወደ ንግድ ሚኒስቴር መዛወር በይፋ በተገለጠ ጊዜ፤ አብዛኛዎቹ ገዥዎች « .... ይኸ ሲባጐ ወደ ንግድ ሄዶ በዚያ ከነጋዴዎች ጋር እየተናነቀ ይኑር .... » የሚል ትችት በመስጠታቸው ነው።

ተፈሪ መኰንን "ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ" ተብለው ከነገሡ በኋላ፤ ጠላት ኢትዮጵያን እስከ ወረረበት እስከ 1928 ዓ.ም ድረስ፤ መኰንን ሀብተወልድ ከበላይ ሚኒስትር ሳይሾምባቸው በዋና ዲሬክተርነት የንግድ ሚኒስቴርን በሚመሩበት ዘመን፤ ከመሳፍንትና ከመኳንንት ጋር ሳይጋጩ በሰላም በመቆየታቸው እንኳንስ የሥራ ጓደኞቻቸውን ይቅርና ንጉሠ ነገሥቱንም ጭምር ሳያስደንቃቸው አልቀረም።

ከበርቴ ከሆኑት ከታላላቆቹ ነጋዴዎች ጋር መልካም ግንኙነት ከዘረጉ በኋላ፤ ለኢትዮጵያ የውጭ ምንዛሪ ገቢ ለማስገኘት የውጭውን ንግድ ማስፋፋት የመኰንን ሀብተወልድ የመጀመሪያ ጥረት ሆነ። የአገራችንን የቡና ምርትና ቆዳዎችን፣ ከነዚህም ጋር ልዩ ልዩ የቅባት እህሎችን በብዛት ወደ ውጭ አገር ለመላክ የንግድና የገንዘብ ሚኒስቴሮች ፎርማሊቲያቸውን እንዲያቃልሉ በማስደረጋቸው፤ ነጋዴዎች በዚህ ሥራ ለመግፋት እጅግ ደስ አላቸው። በዚህ

መሠረት ጠላት ኢትዮጵያን ከመውረሩ ከሁለት ዓመት በፊት፤ ከአገራችን ወደ ውጭ አገሮች የተላኩት ያገር ምርቶች፣ ከውጭ አገር ወደ ኢትዮጵያ ከገቡት ሸቀጣ ሸቀጦች በእጥፍ በመብለጣቸው፤ ለአገራችን ወደ ዐሥር ሚሊዮን ብር የሚጠጋ የውጭ ምንዛሪ መገኘቱ ይነገራል።

የአገራችን የውጭ ምንዛሪ አቅም እያደገ ከሄደ፤ ለሕዝቡ እጅግ አስፈላጊ የሆነውን የጨርቃ ጨርቅ እንዱስትሪ እንዲሁም እንደ መርፌና ክር፣ እንደ ክብሪትና ሻማ፣ የመሳሰሉትን ጥቃቅን ፋብሪካዎች ለማቋቋም፤ መኰንን ሀብተወልድ ብርቱ ምኞት አደረባቸው። በሕንድ አገር የጨርቃ ጨርቅ እንዱስትሪ ካላቸው ከአንዳንድ የውጭ አገር ሰዎች ጋር በመነጋገር፤ በኢትዮጵያ ከሱፍና ከጥጥ ልዩ ልዩ የሆነ የልብስ ጨርቅ በቀላሉ ለመሥራት እንደሚቻል በቂ መረጃ ካገኙ በኋላ፤ ፋብሪካውን ከማቆም በፊት ባለሞያው ቀድሞ እንዲዘጋጅ፤ ውጭ አገር ተልከው በትምህርት ላይ ከሚገኙት ሦስቱ ወንድሞቻቸው መካከል አንዱ፤ ስለ ጨርቃ ጨርቅ እንዱስትሪ አመራር እንዲያጠና በጥብቅ አሳሰቡ። በዚህ መሠረት ወጣቱ አካለወርቅ ሀብተወልድ፤ አባት ሆነው ያሳደጉትን የታላቅ ወንድሙን ምክር ተቀብሎ፤ በግብፅ አገር በሊሴ አሌክሳንድርያ ባካሎሬአውን ካለፈ በኋላ፤ በፈረንሣይ አገር ሙሉዝ (MULHOUSE) በተባለው ከተማ የጨርቃጨርቅ እንዱስትሪ ሥራ አመራር አጥንቶ በዲፕሎም ተመረቀ። ይሁን እንጂ፤ ወጣቱ አካለወርቅ ትምህርቱን ፈጽሞ ወደ አገሩ ሲመለስ፤ ኢትዮጵያ ከፋሽስት ጣልያን ጋር በጦርነት ላይ ትገኝ ስለነበረ፤ ታላቅ ወንድሙ መኰንን እንዳሰቡለት የተማረውን በሥራ ላይ ለማዋል የሚያስችል ዕድል ሳይገጥመው ቀረ።

## የመኰንን ሀብተወልድ ያገር ፍቅር ማኅበርና ዓላማው፤

ጠላት ኢትዮጵያን ለመውጋት በተዘጋጀበት ወራት፤ በሐምሌ 11 ቀን 1927 ዓ.ም፤ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ለኢትዮጵያ ሕዝብ ያገር ፍቅር ማህበርን ያቋቋሙት በመጀመሪያ ደረጃ ለሁለት ዓላማ ነበር። ይኸውም ፩ኛ በዘመናዊ ጦር ማግሽ ሚሊዮን የሚደርሱ ወታደሮቹን አሰልፎ አገራችንን ለመውጋት በመንዝ ላይ የሚገኘው የፋሽስት ጣልያን ዋና ግቡ፤ ከአርባ ዓመታት በፊት ዳግማዊ ምኒልክ አድዋ ላይ ያደረሱበትን ውርደት ለመበቀልና ነፃነታችንን ቀምቶ ቅኝ ግዛቱ ሊያደርገን መሆኑን ለኢትዮጵያ ሕዝብ ለማስረዳት ሲሆን፤ ፪ኛው ደግሞ፤ ጀግናው የኢትዮጵያ ሠራዊት የመጣብንን ጠላት ለመውጋትና ድንበራችንን ለማስከበር፤ የዘመቻውን ጉዞ በቅርቡ ስለሚጀምር፤ መላው የኢትዮጵያ ሕዝብ ባለው አቅምና ባለው ችሎታ፤ ስንቅ እያዘጋጀ ለየሻለቃው ጦር እንዲያቀርብ ለማሳሰብ ነበር።

በዚህ ሐሳብ መሠረት፤ መኰንን ሀብተወልድ ከአክስታቸው ልጅ ከብላታ ታከለ ወልደሐዋርያት፤ በዚያን ጊዜ የአዲስ አበባ ማዘጋጃ ቤት ዲሬክተር ጋር በመተባበር፤ በዳግማዊ ምኒልክ ሐውልት አደባባይ፤ በየሳምንቱ እሁድ በብዙ ሺህ የሚቆጠር ሕዝብ እየተሰበሰበ፤ በኢ.ት.አቆ. ከሐምሌ 11 ቀን 1927 ዓ.ም ጠላት እስከገባበት እስከ ሚያዝያ 23 ቀን 1928 ዓ.ም ድረስ፤ ስለ አንድነትና ስለ አገር ፍቅር ስሜት ከፍ ያለ ትምህርት ሲሰጥ ቆየ። የጦር መሣሪያዎች ፋብሪካ ያለው የፋሽስቱ የሙሶሊኒ መንግሥት፤ የዓለምን የመንግሥታት ማኅበር ሕግ ጥሶ፤ የኢትዮጵያን ሕዝብ ለመጨረስ ያደረገው ዝግጅት መጠን የሌለው መሆኑ እየታወቀ፤ ለነፃነታችን መከላከያ የሚያስፈልገንን የጦር መሣሪያ በገንዘባችን ለመግዛት፤ ንጉሠ ነገሥታችን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የአውሮፓን መንግሥታት ቢጠይቁ፤ መከልከላቸውንና እነዚህም ወዳጅ የተባሉት አገሮች ኢትዮጵያን

ለመርዳት ፈቃደኞች አለመሆናቸውን፤ መኰንን ሀብተወልድ በመረረ ስሜት ሲያስረዱ፤ የተሰበሰበው ሕዝብ ምን ያህል እንዳዘነና ምን ያህል እንደ ተቆጨ፤ መጠኑን ለመለካት የሚቻል አልነበረም። አቶ መኰንን ንግግራቸውን በመቀጠል፤ " ... ኢትዮጵያ አገራችን ዛሬ በደረሰባት ግፍ ከዓለም መንግሥታት ማህበር እውነተኛ ፍርድ አገኛለሁ ብላ አትጠብቅም። እንዲሁም፤ ወዳጅ ከተባሉ አገሮች በዚህ በክፉ ዘመን አጠገቤ የሚቆሙ ይኖራሉ ብላ ተስፋ አታደርግም። ኢትዮጵያ ያለ ፈጣሪዋና ያለ ጀግኖቹ ልጆቿ ማንም ረዳት የሌላት ስለሆነ፤ ለአገራችን ነፃነትና ለአገራችን ክብር መሥዋዕትነትን ለመቀበል መዘጋጀት ያለብን እኛው ነን .... " ካሉ በኋላ፤ የማህበሩ መሥራች ንግግራቸውን የፈጸሙት ከዚህ በሚከተለው ቃል ነበር። " .... ሞት ለማናችንም የማይቀር ጽዋ ነው። በድንገተኛ አደጋ፣ በድንገተኛ ሕመም በቀላሉ ሊደርስ ይችላል። ነገር ግን፤ ለአገር ነፃነትና ክብር መሥዋዕትነትን መቀበል፤ ለፈረንጅ አልገዛም ብሎ ተዋግቶ መሞት፤ እውነተኛው ጽድቅ ነው። እስከ ዛሬም አገራችን ነፃነቷን ይዛ የኖረችው፤ በዚህ ቆራጥ በሆነው ዓላማችን እግዚአብሔር ረድቶን ነው። ዛሬም ፈጣሪያችን ከእኛው ጋር መሆኑን ከልብ እናምንበታለን። እንግዲህ፤ የአገሬ የኢትዮጵያ ሕዝብ ሆይ ! ያለንበት ሁኔታ ከፍተኛ የመከራና የፈተና ዘመን ነው። የምንችል ከሠራዊታችን ጋር ተሰልፈን ጠላታችንን እንውጋ ! የማንችል ለጀግናዎቹ አርበኞቻችን ስንቅ በማቀበል እንርዳ ! ግዴላችሁም አታስቡ፤ እግዚአብሔር ከኛው ጋር ነው። በመጨረሻም ድሉ የኛው ነው።

በዚህ መንፈስና ዓላማ የተመሠረተው የመኰንን ሀብተወልድ የኢትዮጵያ ሕዝብ ያገር ፍቅር ማህበር፤ በየሳምንቱ እሁድ እሁድ በዳግማዊ ምኒልክ አደባባይ እየተሰበሰበ፤ ጠላት አዲስ አበባ እስከገባበት ቀን ድረስ ለዘጠኝ ወራት ባደረገው ጥረት፤ ለኢትዮጵያ ሠራዊት እየተዘጋጀ የቀረበው ስንቅና መድኃኒት መጠኑን ለመለካት ከማይቻልበት ደረጃ ደርሶ እንደነበረ ይነገራል።

ህዳር 18 ቀን 1928 ዓ.ም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ወደ ትልቁ የጦር ሜዳ ወደ ማይጨው ለመዝመት ከአዲስ አበባ ሲነሡ፤ አቶ መኰንን ሀብተወልድን በያዙት ሥራ ላይ የፖስታና የቴሌፎን ቴሌግራፍ ሚኒስቴርን በተጠባባቂነት እንዲመሩ ሾሟቸው። በዚያን ጊዜ ሁለት ዓይነት ኃላፊነት የተሰጠው ይህ ሚኒስቴር፤ የመጀመሪያ ተግባሩ በመላ ኢትዮጵያ የተዘረጉትን የቴሌፎንና የቴሌግራፍ ሥራዎች ማካሄድ ሲሆን፤ ሁለተኛው ደግሞ ዛሬ "የማስታወቂያ ሚኒስቴር" የተባለው መሥሪያ ቤት ስላልነበረ፤ በመንግሥትና በሕዝብ መካከል አገናኝ መኰንን ሆኖ የፕሮፓጋንዳውን ሥራ የሚያከናውን ነበር። በዚህ መሠረት፤ ከፋሽስት ጣልያን ጋር ለሚደረገው ውጊያ የኢትዮጵያ ጦር ጠቅላይ አዛዥ የሆኑት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፤ ደሴ ላይ ካቋቋሙት ዋና መምሪያቸው በየግንባሩ ለተሰለፉት የጦር አዝማቾቻቸው በየጊዜው የሚሰጡት ትዕዛዝ የሚተላለፍላቸው በአዲስ አበባ በኩል ሲሆን፤ እንደዚሁም በየአቅጣጫው የተሰለፉት የጦር አለቆች በየዕለቱ ለንጉሠ ነገሥቱ የሚያቀርቡትን ሪፖርት የሚልኩት በአዲስ አበባ በኩል ነበር። መኰንን ሀብተወልድ ጦርነቱን ደሴ ላይ በሚመሩት በንጉሠ ነገሥቱና በልዩ ልዩ መስመር ሆነው በሚዋጉት የጦር አዛዦቻቸው መካከል የሚለዋወጡትን መልዕክቶች በምሥጢር ከድ እየተቀበሉ፤ በየአድራሻቸው እንዲያስተላልፉ የተሰጣቸው ኃላፊነት፤ እጅግ የከበደ ከመሆኑ የተነሣ እንቅልፍ አጥተው ይሰቃዩ እንደነበረ አብረዋቸው ይሠሩ የነበሩት ሰዎች ሁሉ ምስክርነታቸውን ሰጥተዋል።



መኰንን ሀብተወልድ የስደቱን ሕይወት ለመጀመር ፓሪስ ከተማ እንደደረሱ፤

ከዚህ በቀር ደግሞ፤ ያጋጠማቸው ትልቁ ችግር ሕዝቡ የሚያቀርበውን ጥያቄ መመለስ ነበር።

እንዲህ እንደ ዛሬው ዘመን በራዲዮ የዜና ማሰራጫ ድርጅት ባለመኖሩ፤ በየአቅጣጫው የዘመተው ጦር እስካሁን ምን እንደሠራ፤ ወይም ደግሞ በምን ሁኔታ ላይ እንደሚገኝ ወሬ ለመስማት፤ ከየአውራጃው ወደ አዲስ አበባ የሚጉርፈው ሕዝብ ወሰን የሌለው ሆነ። በዚህ ጊዜ መኰንን ሀብተወልድ ከአክስታቸው ልጅ ከከንቲባ ታከለ ወልደሐዋርያት ጋር በመተባበር፤ ሕዝቡ በየዕለቱ በአዲስ አበባ በዳግማዊ ምኒልክ አደባባይ በቀን አንድ ጊዜ እየተሰበሰበ፤ ስለ ጦርነቱ ሁኔታ የሚጠይቀውን ዜና እንዲያውቅ አደረጉ። ከእንጨት እንደ ፎቅ ሆኖ የተሠራ አንድ ትልቅ መድረክ ላይ እየቆሙ፤ ሕዝቡ መንፈሱ እንዲጸናና እና ለአገር ፍቅርም ያለው ዕምነት በኩራት እንዲጠነክር፤ የኢትዮጵያ ጦር በየዕለቱ ስለሚፈጽመው ጀብዱ በሰፊው ማስረዳት ቀጠሉ። « .... **በንጉሠ ነገሥታችን በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መሪነት፤ በሰሜንና በደቡብ የተሠማሩት ጀግኖቻችን ሥፍር ቁጥር በሌላቸው ዘመናዊ የጦር መሣሪያዎች የታጠቀውንና በአውሮፕላን መርዝ እየነዛ የመጣውን የግፈኛውን የፋሽስት ጦር መክቶ በመዋጋት ላይ ነው** .... » በማለት፤ መኰንን ሀብተወልድ ለሕዝቡ በሚገልጹበት ጊዜ በየመስመሩ የተሰማራው ጦራችን፤ የተምቤኑ ሆነ የአላጌው፣ የሽሬው ሆነ የኦጋዴኑ፣ የባሌው ሆነ የሐረሩ የተቻለውን ያህል ከተዋጋ በኋላ በመዳከም ላይ ይገኝ ነበር። ቀጥሎም ንጉሠ ነገሥቱ ጦራቸው በማይጨው ድል ከሆነ በኋላ፤ ወደ መናገሻ ከተማቸው ተመልሰው ከዚያም ለአቤቱታ ወደ ዤኔቭ የመንግሥታት ማህበር ለመሄድ ጉዞአቸውን እስከ ጀመሩበት ጊዜ ድረስ፤ የመኰንን ሀብተወልድ ፕሮፓጋንዳ በአዲስ አበባና በአካባቢው ፀጥታ እንዳይደፈርስ ምን ያህል እንደመከተ፤ አፈንጉሥ ታከለ ወልደሐዋርያት ለዚህ መጽሐፍ ደራሲ በታህሣሥ 25 ቀን 1953 ዓ.ም በሰጡት ኢንተርቪዩ አስረድተዋል።

ሚያዝያ 23 ቀን 1928 ዓ.ም ሌሊት ንጉሠ ነገሥቱ ከአዲስ አበባ በልዩ ባቡር ተነሥተው ወደ ዤኔቭ ሲጓዙ፤ የንግድ ሚኒስቴርን እና የፖስታ ቴሌፎን ቴሌግራፍ ሚኒስቴርን በተጠባባቂነት ሲመሩ የቆዩት መኰንን ሀብተወልድም፤ ለስደት ወደ ፈረንሣይ አገር ሄዱ።